# ክፍል ፩

# አውሮፓ ! ወደ ሁለተኛው የዓለም ጦርነት

## የኢትዮጵያ ዕድል ምን ይሆን ?

# ምዕራፍ ፩

# የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ውጤትና የሂትለር ሥልጣን መያዝ

የኦስትሪያና የሀንጋሪያ ንጉሠ ነገሥት ፍራንስዋ ዮሴፍና የጀርመን ኢምፓይር መሪ ዳግማዊ ጊዮም፤ በአውሮፓ ውስጥ ግዛታቸውን ለማስፋፋትና የበላይ መሪዎች ለመሆን፤ በፈረንሣይ፣ በእንግሊዝና በመስኮብ መንግሥታት ላይ ከ1914 እስከ 1918 ዓ.ም ድረስ በከፈቱት የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት፤ በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠር ሕዝብ ማለቁንና በብዙ ሚሊያርድ የወርቅ ዶላር የሚገመት ንብረት መጥፋቱን ታሪክ ሁልጊዜ ሲያስታውሰው ይኖራል።

እነዚህ በአውሮፓ ላይ አስተዳደራቸውን በዲክታተርና በፍጹም ፊውዳል ሥርዓት የመሠረቱ የሀብስቡርግ ኦስትሪያና የሆሽንዞለርን ጀርመን ዳይናስቲዎች፤ (Habsbourg and Hohenzollern Dynasty) የዴሞክራሲ አገሮችን፤ በተለይም ፈረንሣይንና እንግሊዝን ለማጥቃት ለሦስት ዓመታት ያህል ባደረጉት ጦርነት፤ እንዳሰቡትና እንደተመኙት ሳይቀናቸው ቀርቷል። እነዚህ ዲክታተሮች የሚያካሂዱት ጦርነት እንደዚሁ ከቀጠለ፤ መዘዙ ለመላው ዓለም ክፉ ጠንቅ እንደሚሆን የአሜሪካ መንግሥት ዘግይቶ ሲረዳው፤ በሚያዝያ 1917 ዓ.ም ከዴሞክራሲ አገሮች ጐን ተሰልፎ ለመዋጋት እርምጃ ወሰደ። የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታትም የአሜሪካንን እርዳታ ሲያገኙ፤ የጦር ኃይላቸውን በማስተባበርና ሞራላቸውን በማጠንከር፤ ለአንድ ዓመት ባደረጉት ብርቱ ጦርነት፤ በህዳር 1918 ዓ.ም የፊውዳሎቹን ጦር ለመደምሰስና ድል ለማድረግ ተቻላቸው።

ለአራት ዓመታት ሰላምን ነስቶ ሲያሰቃይ የኖረው ይህ የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት፤ በዴሞክራሲ አገሮች ድል አድራጊነት ከተፈጸመ በኋላ፤ በፈረንሣይ አገር በቬርሣይ ቤተመንግሥት በአሸናፊዎቹና በተሸናፊዎቹ መካከል በተደረገው የሰላም ውል፤ ያለውዴታቸው በግዴታ በፊውዳሎቹ በአውስትሪያና በጀርመን ነገሥታቶች፤ እንዲሁም በኦቶማን ኢምፓይር ሱልጣን ተጨቁነው ሲገዙ የኖሩት አገሮች ሁሉ፤ ነፃነታቸውንና መብታቸውን ለማግኘት ቻሉ። ከዚህም የተነሳ ከጦርነቱ በፊት የነበረው የአውሮፓ አገሮች ግዛትና የካርታ አቀማመጥ፤ በአዲሱ የሰላም ውል ብዙ ለውጥ ይዞ ቀረበ።

- መስኮብ፤ ኦስትሪያና ጀርመን ተከፋፍለው ለመቶ ዓመታት ሲገዟት የኖረችው ጥንታዊት ፖላንድ፤ የቀድሞዎቹ ግዛቶቿ ሁሉ ተመልሰውላት ነፃ መንግሥት ሆና ተቋቋመች።

- በኦስትሪያና በጀርመን ኢምፓይር ውስጥ በጭቆና እየተገዙ የኖሩት፤ የቼክና የስሎቫኪያ ሕዝቦች በአንድነት ተዋህደው፤ " ቼኮስሎቫኪያ " የተባለ አዲስ ነፃ መንግሥት እንዲያቋቁሙ ተደረገ።

- የቀድሞው የሴርቢያ መንግሥት፤ በኦስትሪያና በሀንጋሪያ ኢምፓይር ተይዘው የነበሩት፤ የሞንቴኔግሮ፤ የክሮዋሲና የዳልማሲ አውራጃዎች ተጨምረውለት፤ "ዩጉዝላቪያ" በሚል ስም አዲሱን መንግሥት አቋቋመ።

- የኦስትሪያና የሀንጋሪያ ዳይናስቲዎች በሰፊው ይዘውት የነበረው ግዛት ሁሉ ስለተወሰደባቸው፤ ከእንግዲህ ወዲህ እነዚህ ሁለት አገሮች (ኦስትሪያና ሀንጋሪያ) ተለያይተው፤ እያንዳንዳቸው ለየብቻቸው መጠነኛ በሆኑት ቀሪዎቹ ግዛቶቻቸው ላይ፤ የሬፑብሊክ አስተዳደር መንግሥት መስርተው እንዲኖሩ ተፈቀደላቸው።

እንግዲህ ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፤ ሀብስቡርግ (Habsbourg) የተባለው የኦስትሪያና የሀንጋሪያ ዳይናስቲ ፈራርሶ፤ በውስጣቸው የነበሩት አገሮች ሁሉ፤ ነፃነታቸውን አግኝተው በዴሞክራሲ ሥርዓት እንዲተዳደሩ ከተወሰነ በኋላ፤ ድል አድራጊዎቹ መንግሥታት ፈረንሣይና እንግሊዝ፤ አሜሪካና ጣልያን በትልቁ ጥፋተኛ በጀርመን ላይ የመሰላቸውን ፍርድ ለመስጠት ሜዳው ሰፊ ሆኖ ቀረበላቸው። በተለይ ፈረንሣይ፤ የጀርመን ንጉሠ ነገሥት የዳግማዊ ጊዮም ጦር ለአራት ዓመታት እጅግ አድርጐ ያደቀቃትና፤ ወደ አንድ ሚሊዮን ተኩል የሚጠጉ ሕዝቦቿን የጨረሰባት ስለሆነ፤ በዚህ ተወዳዳሪ በሌለው ጨካኝ መንግሥት ላይ ብድሩን መመለስ ያስፈልጋል በማለት ቆርጣ ተነሳች። ሌሎቹ ከፈረንሣይ ጋር ሆነው የጦርነቱ ተካፋዮችና ድል አድራጊዎች የተባሉት፤ የአሜሪካ፣ የእንግሊዝና የጣልያን መንግሥታት ደግሞ በነበራቸው አመለካከት፤ ምንም እንኳን በዓለም ላይ ይህ ሁሉ ዕልቂት የደረሰው፤ በዲክታተሩ በጀርመኑ መሪና በተከታዮቹ ሕዝቦች መሆኑ ባይካድም፤ እንደ ፈረንሣይ ምኞት፤ ይህን አስቸጋሪ አገር አሸናፊዎቹ ተከፋፍለው ለተወሰነ ዓመታት እንዲገዙት ማድረግ የተገባ ሆኖ አልታያቸውም።

እንደሚታወቀው፤ ፈረንሣይ ከሌሎቹ አገሮች ይበልጥ በጀርመን ዕብሪት የተደጋገሙ ጥቃቶች የደረሱባትና መከራን ብቻ ሳይሆን ውርደትንም የተቀበለችበት ጊዜ ስለነበረ፤ አጋጣሚውን ዕድል ስታገኝ ያለፈ ብድሯን ሁሉ ያለ ገደብ ለመመለስ መፈለጓ፤ ሊያስደንቅ አይችልም። ለምሣሌ ያህል፤ እ.ኤ.አ በ1871 ዓ.ም ቢዝማርክ (Bismarck) የታወቀው የጀርመን የፖለቲካ መሪ፤ የፈረንሣዩን የናፖሊዮንን ሣልሳዊ መንግሥት በጦር ወግቶ በማሸነፍ፤ በስተምሥራቅ ፈረንሣይ የሚገኙትን ሎሬንና አልዛስ (Alsace-Lorraine) የተባሉትን ሁለት አውራጃዎች ነጥቆ ወደ ጀርመን ግዛት አስገባቸው። ቢዝማርክ፤ በዚህ ብቻ አልቆመም። ከፓሪስ ከተማ በስተደቡብ በኩል አሥራ አራት ኪሎ ሜትር ርቆ የሚገኘውን " ቬርሣይ " (Versailles) የተባለውን የፈረንሣይ ቤተመንግሥት በጦር ኃይል ይዞ፤ ከአሥራ አራተኛው ሉዊ (Louis 14) ዘመን ጀምሮ የተከበረውን የዙፋን አዳራሽ በማስከፈት፤ የጀርመን አንድነት አገሮች ንጉሠ ነገሥት እንዲሆን የተመረጠው ቀዳማዊ ጊዮም (Empereur Guillaume Premier) ሥርዓተ ንግሡ እንዲፈጸምበት አደረገ። ይህ የቢዝማርክ አሠራር ምን ያህል በዕብሪትና በማን አለብኝ መንፈስ የተደረገ መሆኑ ለማንም ግልጽ ነው። በጉልበቱ የተማመነ መሪ የአንድን ነፃ አገር ቤተመንግሥት አስከፍቶ የሥርዓተ ንግሥ ማስፈጸሚያ ሲያስደርገው፤ ለተጠቂው አገር ምን ያህል አሳዛኝ ውርደት መሆኑ የተሰወረ አይደለም። ከዚህ ጊዜ ጀምሮ ጀርመኖች አንድነታቸው የተመሰረተበት ታሪካቸው በሚወሳበት ጊዜ፤ ዕድሜ ለጀግናው ቢዝማርክ የመጀመሪያው ንጉሠ ነገሥታቸው ቀዳማዊ ጊዮም የሥርዓተ ንግሡ በዓል የተከናወነው በፈረንሣይ ቬርሣይ ቤተመንግሥት ውስጥ ነው እየተባለ

ይነገርለታል። አሁን ደግሞ ከአርባ ሦስት ዓመታት በኋላ፤ ይኸው የሆኸንዞለርን (HohenZollern) ዳይናስቲ ንጉሠ ነገሥት ዳግማዊ ጊዮም፤ የአባቱን መንፈስ ተከትሎ በዚች አገር ላይ በጦርነት ያደረሰባት ጉዳት እጅግ የከበደ ስለሆነ፤ ከእንግዲህ ወዲህ ይህንን ጀርመን የተባለ የክፉዎች አገር አድቅቆ እንደገና እንዳያንሰራራ ከማድረግ በስተቀር፤ ሌላ መንገድ የለም ብላ ፈረንሣይ የበኩሏን ውሳኔ አድርጋ ነበር።

ጀርመን ድል ሆኖ የተሸናፊነቱን የጦር ስምምነት ከፈረመ በኋላ፤ በፈረንሣይ አገር ቬርሣይ በተባለው ዝነኛው ቤተመንግሥት ውስጥ በተደረገው የሰላም ጉባኤ ላይ ዋና ዋናዎቹ የእንግሊዝና የፈረንሣይ፤ የአሜሪካና የጣልያን መሪዎች፤ በመጨረሻ ተስማምተው ጥፋተኛ ተብሎ በተፈረደበት በዚህ አገር ላይ እጅግ የከበደ ቅጣት ወሰኑበት። ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ በመጀመሪያው ሰሞን እንግሊዝና አሜሪካ በጀርመን ላይ የሚፈረደው ቅጣት፤ አገሩንና ሕዝቡን የሚጉዳ መሆን የለበትም የሚል አቋም አሳይተው ነበር። ነገር ግን፤ ከአለፉት አርባ ዓመታት ወዲህ በጀርመን ግፈኛነት ሁለት ጊዜ በጦርነት የተጠቃችው ፈረንሣይ፤ የአንግሎ ሳክሶኖችን ሐሳብ የምትቀበል አልሆነችም። ስለዚህ፤ እንግሊዝና አሜሪካ በመጀመሪያው ስሜታቸው ሊገፉበት ስላልቻሉ፤ ፈረንሣይ ካቀረበቻቸው የቅጣት ሐሳቦች፤ ከመቶ ሰማንያውን ያህል በመቀበላቸው፤ እ.ኤ.አ ሰኔ 28 ቀን 1919 ዓ.ም በተደረገው ስምምነት፤ በጀርመን ላይ የሚከተሉት እርምጃዎች ተወሰዱ።

1. በአውሮፓ ውስጥ ጀርመን ኃይሉን ተመርኩዞ፤ በጦርነትና በሌላም ጉዳና በማስፈራራት ከየመንግሥታቱ እየነጠቀ የያዛቸው፤ በጠቅላላው ስልሣ ስምንት ሺህ እስኳር ኪሎ ሜትር ስፋት ያላቸውን ልዩ ልዩ አውራጃዎች፤ ከስምንት ሚሊዮን ነዋሪ ሕዝቦቻቸው ጋር፤ ጥንት ወደነበሩበት የትውልድ አገራቸው እንዲመለሱ ወሰኑበት። ከነዚህም ውስጥ፤ ከአርባ ዓመታት በፊት ከፈረንሣይ መንግሥት ላይ የተወሰዱት አልዛስና ሎሬን (Alsace Lorraine) የተባሉት አውራጃዎች ይገኙበታል።

2. ጀርመን በአፍሪካና በፓስፊክ ውስጥ በቅኝ ግዛት የያዛቸው አገሮች፦

ሀ) ካሜሩንና ቶጐ ለፈረንሣይና ለእንግሊዝ መንግሥታት፤
ለ) ሩዋንዳና ቡሩንዲ ለቤልጊክ መንግሥት፤
ሐ) ዛሬ ናሚቢያ የተባለው የደቡብ ምዕራብ አፍሪካ፤ ለደቡብ አፍሪካ መንግሥት፤
መ) በፓሲፊክ የሚገኙት ደሴቶች ለጃፓን፤ ለአውስትራሊያና ለኒውዚላንድ፤ ተደልድለው እንዲሰጡ ተደረገ።

3. ጀርመን እነዚህ ሁሉ አገሮች ከተቀነሱበት በኋላ፤ በአውሮፓ በሚቀረው ግዛቱ ላይ የሬፑብሊክ አስተዳደር መንግሥት ለመመሥረት ሲፈቀድለት፤ ከእንግዲህ ወዲህ፤ ቀድሞ እንደነበረው፤ የምድር፣ የአየር ኃይልና የባሕር ኃይል የጦር ድርጅቶች ለማቋቋም የተከለከለ መሆኑ ተወሰነበት። ነገር ግን፤ የሬፑብሊኩን መንግሥት ከመሰረተ በኋላ፤ ለፀጥታው መጠባበቂያ ከአንድ መቶ ሺህ የማይበልጡ ወታደሮችና መኰንኖች ብቻ ለማቋቋም እንደሚፈቀድለት ተነገረው።

4. በዚህ በመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ላይ ለደረሰው ዕልቂት ሁሉ ዋና ተጠያቂው ጀርመን ነው ተብሎ ስለተፈረደበት፣ አንድ መቶ ስላሣ ሁለት ሚሊያርድ የወርቅ ማርክ፣ ለድል አድራጊዎቹ አገሮች በተለይም በይበልጥ ለተጐዳችው ፈረንሣይ ካሣ እንዲከፍል በቬርሣይ የተቋቋመው የጦር ካሣ ጉዳይ ኮሚሲዮን ፍርዱን ሰጠ።

ከዚህ በላይ እንደታየው ድል አድራጊዎቹ መንግሥታት፣ በጀርመን ላይ የወሰኑበት ቅጣት ምን ያህል ከባድ መሆኑንና፣ የኢኮኖሚ ልማቱን የሚያካሂድባቸው ግዛቶቹ ሁሉ ከተወሰዱበት በኋላ፣ ይህን ሁሉ የጦር ካሣ ዕዳ ለመክፈል እንዴት እንደሚችል አላሰቡለትም። በአገራችን አነጋገር፣ የወደቀ ዛፍ ምሣር ይበዛበታል እየተባለ እንደሚነገረው፣ ድል አድራጊዎቹ በጀርመን ላይ እያደራረቡ የወሰዷቸው የቅጣት እርምጃዎች ሁሉ፣ ሰብዓዊነትንና ትክክለኛ ፍርድን የተመረኮዙ ሆነው አልተገኙም። ከሁሉም ይበልጥ በጀርመን ሕዝብ ላይ ከባድ አደጋ እንደወደቀበት ሆኖ የታየው፣ ለጦር ካሣ የተደረገው ተመንና አከፋፈል ጉዳይ ነበር።

እ.ኤ.አ በ1920 ዓ.ም ሚስተር ከይነስ (Mr. Keynes) የተባለው የእንግሊዝ ኢኮኖሚስት ሰፊ ጥናት አድርጐ አንድ የተለየ አስተያየት አቀረበ። የቬርሣይ የጦር ካሣ ኮሚሲዮን የወሰነው አንድ መቶ ሰላሣ ሁለት ሚሊያርድ የወርቅ ማርክ፣ በአንድ በኩል የጀርመንን ሕዝብ እጅግ ከፍ ያለ ውድቀት ላይ የሚጥለው ሲሆን፣ በሌላ በኩል ደግሞ ካሣ ተቀባዮቹ ፈረንሣይና እንግሊዝ በሚያገኙት ገንዘብ፣ የአገሮቻቸውን ኢኮኖሚ ለመገንባት ከሚያልሙት ይልቅ፣ የሚደርስባቸው ጉዳት ሊበልጥ ይችላል። ስለዚህ፣ የጦር ካሣው ሂሣብ መተመን ያለበት የጀርመን ሕዝብ በየዓመቱ በሚያመርተው መጠን እንዲሆን የግዴታ አስፈላጊ ነው ሲል፣ እንግሊዛዊው ኢኮኖሚስት በጥብቅ አሳሰበ። እንግሊዞች ችግሩን ተረድተው የኢኮኖሚስቱን ሐሳብ ለመቀበል ሲዘጋጁ፣ ፈረንሣዮች ደግሞ ቀደም ሲል በኮሚሲዮኑ የተወሰነው የጦር ካሣ (132 ሚሊያርድ) አይቀነስም ብለው አስቸገሩ።

አዲስ የተቋቋመው የጀርመን ሬፑብሊክ መንግሥት እንኳንስ ፈረንሣዮች እንደሚፈልጉት የጦሩን ካሣ ለመክፈል ይቅርና፣ በአገሩ ላይ በደረሰበት ከባድ የኢኮኖሚ ውድቀት ምክንያት፣ ለሕዝቡ የሚያስፈልገውን ምግብ እንኳን ለማቅረብ አልቻለም። ይህን ችግር በማየት " ዳወስ " (Dawes) የተባለ አሜሪካዊ ኤክስፐርት የራሱን ጥናት ካካሄደ በኋላ፣ የጀርመን ሬፑብሊክ መንግሥት ለጊዜው በየዓመቱ በግምት ከአንድ እስከ ሁለት ሚሊያርድ ተኩል (1-2.5 Milliard) የሚደርስ የወርቅ ማርክ ለጦር ካሣው እየከፈለ ቢቆይና፣ ወደፊት የአገሩ የኢኮኖሚ ልማት በሚፈቅድለት መጠን ታይቶ፣ እስከምን ያህል ድረስ መክፈል እንደሚገባው ተጠንቶ ቢወሰን ይሻላል የሚል ሐሳብ አቀረበ። ይህንን ፕላን እንግሊዞች ቀና በሆነ መንፈስ ሲመለከቱት፣ እንደተለመደው ፈረንሣዮች አንቀበለውም አሉ። እንዲሁም፣ የጀርመን ሕዝብ መንግሥታችን ይህን ሐሳብ መቀበል የለበትም በማለት በያለበት ሰላማዊ ሰልፍ አደረገ። በተለይም ወጣቱ ናዚስት ዮሴፍ ጐበልስ (Joseph Gobbels) የዳወስ ፕላን፣ ጀርመንን ዘለዓለማዊ ድህነት ላይ የሚጥላት ነው በሚል መፈክር፣ የሕዝቡን ተቃውሞ አባባሰው። ከዚህ በኋላ፣ ጥቂት ጊዜ ቆይቶ ሚስተር አውን ያንግ (Owen Young) የተባለ ሌላ አሜሪካዊ የፖለቲካና የፋይናንስ አዋቂ፣ ስለጦር ካሣው አከፋፈል ጉዳይ የዳወስን ፕላን እንደሚከተለው አሻሽሎ አቀረበው።

1ኛ/ በቬርሣይ ኮሚሲዮን ተወስኖ የነበረው 132 ሚሊያርድ ወርቅ ማርክ፤ ከጀርመን አቅም በላይ ስለሆነ፤ ሂሣቡ ተቀንሶ 38 ሚሊያርድ ወርቅ ማርክ እንዲሆን፤

2ኛ/ ይህ ሰላሣ ስምንቱ ሚሊያርድ የወርቅ ማርክ ደግሞ ተከፍሎ የሚያልቀው ከሚቀጥሉት ሰላሣ ስድስት (36) ዓመታት በኋላ እንዲሆን፤

የሚል ነበር። ትልቁን የጦር ካሣ እንዲያገኝ የተፈረደለት የፈረንሣይ መንግሥት፤ ስለአከፋፈሉም ሆነ ስለሚከፈለው ገንዘብ ልክ፤ በየጊዜው የሚቀርብለትን ሐሳብ አልስማማም እያለ ብዙ ጊዜ ከፈጀ በኋላ፤ አሁን በመጨረሻ የተጠናውን የሚስተር ያንግን ፕላን መቀበል ግዴታው ሆነ። የጀርመን ሬፑብሊክ መንግሥትም በበኩሉ፤ ይህንን የተወሰነውን የሰላሣ ስድስት ዓመታት ዕዳ ለመክፈል ተስማምቶ ከድል አድራጊዎቹ መንግሥታት ጋር ውል ሲፈርም፤ በእነ ጉበል መሪነት የሕዝቡ ተቃውሞ እጅግ የጠነከረ ሆኖበት ነበር። ወጣቱ ናዚስት ዮሴፍ ጉበል፤ ለጀርመን ሕዝብና ለአውሮፖው ዓለም በሚያሠራጨው የተቃውሞ መግለጫ፤ " ... **የያንግን ፕላን ተቀብሎ ማፅደቅ፤ ወደፊት ገና ባልተወለዱት የጀርመን ልጆች ላይ የሞት ፍርድ ሰጥቶ እንደመጠበቅ የሚቆጠር ነው** ... " አለ።

ዶክተር ጉበል በዚህ በጣም በሚማርከው ፕሮፓጋንዳው፤ ምንም እንኳ የያንግን ፕላን እንዳይፀድቅ ለማድረግ ባይሳካለትም፤ በሚሊዮን የሚቆጠረውን የጀርመንን ሕዝብ አሰልፎ ለማውገዝና ወደፊት የሂትለር የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ ምን ጥቅም እንደሚያስገኝ ደጋፊዎች ለመሰብሰብ ጥሩ ዕድል ሰጥቶታል።

## ጀርመን ወደ ሂትለር ቀንበር

የመጀመሪያው ዓለም ጦርነት ከተፈጸመ በኋላ፤ የታወቀው የሆኸንዞለርን ዳይናስቲ ተወላጅ፤ የዲክታተሩ የዳግማዊ ጊዮም አገዛዝ ፈርሶ የሬፑብሊክ አስተዳደር በመመስረቱ፤ እጅግ አብዛኛው የሆነውን የጀርመንን ሕዝብ የሚያስደስት እንጂ፤ ቅር የሚያሰኝ አልነበረም። የጀርመንን ሕዝብ እጅግ ከመረረ ሀዘን ላይ የጣለው፤ መሪዎቹ ባደረሱት ጥፋት በግዴታ እየታዘዘ ተግባሩን በፈጸመውና በሌላውም በምንም ጉዳይ ውስጥ ተካፋይ ባልሆነው ሰላማዊ ሕዝብ ላይ፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት በቬርሣይ ስብሰባቸው የወሰኑበት ብርቱ ቅጣት ነው። የሆኸንዞለርን ዳይናስቲ ንጉሠ ነገሥትና አብረውት የተሰለፉት የጦርና የሲቪል ባለሥልጣኖች፤ በዓለም ላይ ጦርነቱን አስነስተው በሰው ልጆች ሕይወትና በአገር ንብረቶች ላይ ባደረሱት ጥፋት ተጠያቂዎቹ መሪዎቹ እንጂ፤ ሕዝቡ ምን አደረገ ? ... በዚህ በተነሳው የዓለም ጦርነት ምክንያት፤ ከደረሰው ዕልቂትና መከራ የጀርመን ሕዝብ ለብቻው ተለይቶ እንዳልዳነ ለማንም ግልጽ ነው። **ፈረንሣይ እስከ አንድ ሚሊዮን አምስት መቶ ሺህ የሚደርሱ ልጆቿን አጥታለች እየተባለ ሲነገርላት፤ ጀርመንም ከአንድ ሚሊዮን ስምንት መቶ ሺህ በላይ የሆኑት ዜጐቿ እንደሞቱባት መረሳት የለበትም።** የዚህ ሁሉ ጣጣ አመንጭውና ጥፋተኛው ጀርመን ነው እየተባለ የፍርድ ነጋሪት ሲመታ፤ በጀርመን መንግሥትና በጀርመን ሕዝብ መካከል ያለውን የኃላፊነት ልዩነት ማተኮር የተገባ በሆነ ነበር። ሕዝብ የሚፈጽመው ሁሉ ከመሪዎቹ በግዴታ የታዘዘውን እንጂ፤ ራሱ ሐሳቡን አፍልቆ ራሱ የወሰነውን አለመሆኑን የሚስተው የለም።

ነገር ግን፤ እጅግ የሚያሳዝነው ይህን ሁሉ የጦርነት እሳት የጫሩትና ያነደዱት የመንግሥት መሪዎች እነ ዳግማዊ ጊዮምና እነ ፍራንስዋ ዮሴፍ ድል ከሆኑ በኋላ፤ ከእነ ረዳቶቻቸው በጎረቤት አገሮች የፖለቲካ ጥገኝነትን እየተቀበሉ የተደላደለ የምቾት ሕይወት ሲያገኙ፤ እነሱ ባደረሱት ጥፋት እጅግ መራራ የሆነውን ቅጣት እየተቀበለ ለብዙ ዘመናት በስቃይ እንዲኖር የተፈረደበት የጀርመን ሕዝብ ነው። ስለዚህ፤ በተለይ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት በዚህ የጭካኔ ፍርድ በሰጡበት በጀርመን ሕዝብ ላይ ያደረሱበትን ግፍ፤ አጸፋውን የሚከፍሉበት ጊዜ ሩቅ አይደለም በማለት፤ ናሽናል ሶሲያሊስት (ናዚ) የተባለው አዶልፍ ሂትለር የመሰረተው ፓርቲ በየዕለቱ በሚያሠራጭለት ፕሮፓጋንዳ፤ ሕዝቡ እየተማረከ ይህን ተስፋ እውን ሆኖ የሚያይበትን ቀን በናፍቆት መጠባበቅ ጀመረ።

እንደሚታወቀው አንድ ሕዝብ ብሶቱን አስማምረው ሲያቀርቡለትና፤ ለመልካም ውጤቱ አብረኸን ተጓዝ ካሉት፤ ተስፋውን በመጓጓት የተጠየቀውን ለመፈጸም ወደ ኋላ አይልም። የሂትለር ፓርቲ የፕሮፓጋንዳው መሪዎች እነ ዶክተር ጐበል በቀለጠፈና በጠለቀ ዘዴ በየዕለቱ የሚሰጡት ገለጻ፤ የሕዝቡን መንፈስ የሚማርክና ተስፋውን የሚያዳብር ነበር። " ... የጀርመን ሕዝብ በጦርነቱ ድል ሆኗል መባሉ ወይም መሆኑ የሚያሳፍረው ወይም የሚቆጨው አይሆንም። ጦርነቱ በጀርመን ሕዝብ ፍላጐትና በጀርመን ሕዝብ ፈቃድ የተደረገ አይደለም። የጥቂቶች የፊውዳሎችና የዲክታተሮች ነገሥታት ፍላጐትና ምኞት ነው። የጦርነቱ ባለቤቶች እነማን መሆናቸው በግልጽ እየታያቸው፤ ፈረንሣዮችና እንግሊዞች፤ በተለይም ፈረንሣይ፤ ይህን የፈረዱበትን የጀርመን ሕዝብ መብቱን ገፍፈው፤ እንደ ባሪያ ሊገዙት በመወሰናቸው እኛን ጀርመኖችን ብቻ ሳይሆን፤ መላውን የዓለም ሕዝብ እጅግ አድርጐ አሳዝኗል። ይሁን እንጂ፤ እኛ ጀርመኖች አለአግባብ የወደቀብንን መከራ ችሎ የማሳለፍና ብድሩንም የመመለስ ጥንካሬያችንና ችሎታችን ደካማ አለመሆኑን፤ ባላጋራዎቻችን ቢገነዘቡት ጥሩ ነበር። ነገር ግን፤ ዛሬ ለመገንዘብ ያቃታቸውን፤ ነገ ሳይወዱ በግዱታቸው አሜን ብለው እንደሚቀበሉት እርግጠኞች ነን። ባላጋራዎቻችን የሚጫወቱብንና የሚያስቃዩን ለተወሰነ ጊዜ ብቻ ነው። ከዚያ በኋላ ግን፤ ይህ ሁሉ ያልፍና ደህና አድርገው እንዲያዩት ብቻ ሳይሆን፤ ተራው ደርሷቸው መራራውንም ችግር እንዲቀምሱት ይደርጋል ... " የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ ይህን የመሰለውን ፕሮፓጋንዳ ለአራት ዓመታት ባለማቋረጥ ሲነዛ የኖረ በመሆኑ፤ የጀርመን ሕዝብ የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ድል አድራጊዎች በሆኑት መንግሥታት፤ በተለይም በፈረንሣይ ላይ ብርቱ ቂም አሳድሮ፤ ብድሩን የሚከፍልለት መሪ ለማግኘት እንዲጥር አስደርጐታል።

## ብድር መላሹ መሪ
## አዶልፍ ሂትለር፤ ከየት ተነሣ ?

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የነበሩት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዘመነ መንግሥታቸው፤ የውጭ አገር ጋዜጠኞች " ... ከእርስዎ በኋላ አገርዎን ማን ይመራት ይመስልዎታል ? ... " በማለት ሲጠይቋቸው የሚሰጡት መልስ፤ " ... እኛ ልጃችን ወራሻችን ይሆናል ብለን ሕገ መንግሥቱን አጽድቀናል። ነገር ግን፤ ፈጻሚው እግዚአብሔር ስለሆነ፤ ከእኛ በኋላ ልጃችን ወይም እግዚአብሔር የመረጠው ሰው ይሆናል ብለን እናምናለን ... " ይሉ ነበር። እንደሚታየው የጃንሆይ አስተሳሰብ አንድ ሰው ለአንድ አገር መሪ መሆን የሚችለው፤ በዘውድ

ሥርዓት ከሆነ በውርስ፤ የዴሞክራሲን መንገድ ከተከተለ በሕዝብ ምርጫ፤ በጉልበት ከሆነ ደግሞ በኩ-ዴታ ሊከናወን ይችላል ቢባልም፤ **ማናቸውም ያለ እግዚአብሔር ፈቃድ አይፈጸምም የሚል ነው።** ይህንን መሰረት አድርገን በአገራችን የደረሰውን ታሪክ ስንመለከት፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በጨካኞቹ ከመገደላቸው ከዘጠኝ ዓመታት በፊት የተናገሩት ቃል በትክክል ደርሶ ታይቷል። የእግዚአብሔር ቁጣና ተዓምር ባይጨመርበት፤ የደርግ ቡድን በድንገት ተነስቶ ለአሥራ ሰባት ዓመታት ኢትዮጵያን እንደአሰኘው ይገዛታል ተብሎ የተጠበቀ አልነበረም። እንደዚሁም፤ **አዶልፍ ሂትለር የጀርመን መሪ ለመሆን ከምን እንደተነሳና ከዚያም አልፎ ዓለምን ለመበጥበጥ የወሰዳቸው እርምጃዎች ሁሉ ሲታዩ፤ ተዓምር ነው ከማለት በስተቀር ሌላ ትርጉም አይገኝላቸውም።**

አዶልፍ ሂትለር እ.ኤ.አ ሚያዝያ 20 ቀን 1889 ዓ.ም በጀርመንና በኦስትሪያ ግዛት ድንበር ላይ በምትገኝ በአንዲት " የላኛዋ ኦስትሪያ " (Haute-Autriche) በምትባል ትንሽ ከተማ ውስጥ ተወለደ። አባቱ **አልዋ ሂትለር** (Alois Hitler) የመንግሥት ጉምሩክ ሠራተኛ ሆኖ በሚያገለግልበት ዘመን፤ ዕድሜው ከገፋ በኋላ ትዳር መስርቶ ከወለዳቸው ከስድስት ልጆቹ መካከል በሕይወት ያደጉለት የመጨረሻዎቹ አዶልፍና ከእሱ የምትቀጥለው እህቱ ፓውላ (Paula) ነች። አዶልፍ በተወለደ በአሥራ ሁለት ዓመቱ አባቱ በድንገት ሲሞትበት፤ ከሦስት ዓመት በኋላ ደግሞ እናቱም በሕመም አረፈች። ከዚህ በኋላ፤ አዶልፍና እህቱ ፓውላ " **የሙት ልጆች** " እየተባሉ ከኦስትሪያ መንግሥት የመኖሪያና የመማሪያ እርዳታ እያገኙ ሲኖሩ፤ አዶልፍ በትምህርት ረገድ ደካማ ከመሆኑ የተነሳ፤ ወደ ከፍተኛ ደረጃ ለመድረስ ሳይችል ቀረ። አዶልፍ የፈለገው፤ ቪየና በሚገኘው የኪነ ጥበብ አካዳሚ ገብቶ የሰዓሊነት ሞያ ለመማር ስለነበረ፤ የመግቢያውን ፈተና ሁለት ጊዜ ተወዳድሮ ባለማለፉ ከፍ ያለ ብስጭት ላይ ወድቆ ነበር። ከዚህ ቀጥሎ ደግሞ አርክቴክት (Architect) ለመሆን ፈልጎ ያደረገው ሙከራ አልተሳካለትም። ነገር ግን በልጅነቱ ዘመን ያገር ውበት የሚያሳዩ ልዩ ልዩ ስዕሎች መንደፍ ይወድ ስለነበረ፤ በዚህ ዝንባሌው አንዳንድ ምስሎችን እየሳለ በመሸጥ፤ የኑሮ መደገፊያ ሆኖለት ነበር። አዶልፍ፤ ሲመኘው እንደነበረው የአካዳሚ ትምህርት ለማግኘት ባይታደልም፤ የታወቁትን ልዩ ልዩ የፊሎዞፊ መጻሕፍቶችን በማንበብ አእምሮውን ያበለጽግ እንደነበረ ይነገርለታል።

በልጅነቱ ዘመን በችግር የተጉላላና የወደፊት ዕድሉም ምን እንደሚሆን ማወቅ ያልቻለው ወጣት፤ ዕድሜው ሀያ አምስት ዓመት ሲሞላው፤ በ1914 ዓ.ም በተነሳው የዓለም ጦርነት በወዶ ዘማችነት ተመዝግቦ፤ ለጉረቤት አገሩ ለጀርመን በመሰለፍ በጦር ሜዳ ላይ ዋለ። አንድ ዓመት ያህል እንደተዋጋ፤ የአምሳ አለቅነት ማዕረግ ለማግኘት ቻለ። የአምሳ አለቃ ሂትለር፤ በጦሩ ሜዳ ላይ ባሳየው የውትድርና ሞያ፤ " **አንደኛ ደረጃ የብረት መስቀል** " የተባለውን ኒሻን ተሸለመ። (Croix De Fer Premiere Classe) ጀርመን ድል ሆኖ የጦር ማቆሚያውን ስምምነት ከመፈረሙ ጥቂት ሳምንታት በፊት፤ የእንግሊዝ አየር ኃይል በረጨው የመርዝ ጋዝ፤ የአምሳ አለቃ ሂትለር ዓይኑ ስለቆሰለበት፤ ከጦሩ ሜዳ ወደ ሙኒክ ተከማ ተወስዶ በዚያ በሚገኝ ሆስፒታል ሲታከም ቆየ።

አዶልፍ ሂትለር፤ የትውልድ አገሩ የሆነው ኦስትሪያና በጦር ሜዳ የተሰለፈለት የጉረቤት አገሩ ጀርመን፤ ድል ሆነው የጦርነቱ ፍጻሜ እንደታወጀ፤ ጊዜያዊ ቅጥር ካገኘበት ከወታደርነቱ በገዛ ፈቃዱ ተሰናብቶ ወደ ፖለቲካ ሥራ

ለማምራት ወሰነ። ወዲያውም አንድ የእናጧኒነት ሞያ ያለው ሚስተር ድሬክስለር (Mr. Drexler) የተባለ የጀርመን ዜጋ፤ ቀደም ሲል ባቋቋመው የሠራተኞች የመብት አስከባሪ ማህበር ውስጥ፤ አዶልፍ ሂትለር አባል ከሆነ በኋላ፤ በጥቂት ጊዜ ውስጥ ለማህበሩ ዕድገት ባሳየው ጥረት፤ በአባሎቹ ዘንድ ከፍ ያለ አድናቆትን አተረፈ። ከጥቂት ወራት በኋላ ደግሞ፤ ይህ የሠራተኞች መብት አስከባሪ እንዲሆን የተቋቋመው ማህበር፤ የጀርመኖች የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ ተብሎ እንዲሰየም አዶልፍ ያቀረበውን ሐሳብ አባሎቹ በሙሉ ተቀበሉት። ከዚያም ጊዜ ሳይፈጅ፤ የቀድሞውን ሊቀመንበር ሚስተር ድሬክስለርን እንዲሻር አስደርጎ፤ እሱ ራሱ የፓርቲው ዋና ጸሐፊና የበላይ ፕሬዚዳንት እንዲሆን አሳወጀ።

እንግዲህ ! ከዚህ የታሪክ አመጣጥ እንደምንረዳው፤ ይህ " ናሽናል ሶሲያሊስት " የተባለው ፓርቲ በ1921 ዓ.ም የተወለደ ቢሆንም፤ ከመንግሥት ዕውቅና እስኪሰጠው ድረስ፤ ለስድስት ዓመታት ሥራውን ሲያከናውን የቆየው በስውር ጉዳና እንጂ፤ በይፋ አልነበረም። ለዚህም ትልቅ ችግር የሆነው፤ አዶልፍ ሂትለር የኦስትሪያ ተወላጅና ዜጋ ሆኖ፤ ለጀርመን ሕዝብ የፖለቲካ ፓርቲ መስራችና ታጋይ ለመሆን እንዴት ይችላል ? የሚለው ጥያቄ ነበር። ለዚህ መፍትሔ ብዙ ጥናት ሲደረግ ከቆየ በኋላ፤ አዶልፍ ሂትለር ሚያዝያ 30 ቀን 1925 ዓ.ም አገር ግዛት ሚኒስቴር ቀርቦ፤ " **እኔ ዜግነት የሌለኝ** (**አገር አልባ**) **ስለሆንኩ፤ የጀርመን ዜግነት ይሰጠኝ ...** " ሲል አመለከተ። በዚያን ዘመን በልማድ እንደሚሠራው አንድ አውሮፓዊ፤ <u>**አገር አልባ ነኝ**</u> ብሎ እግሩ ያረፈበት አገር ዜግነት እንዲሰጠው ሲያመለክት፤ አፈጻጸሙ ጊዜ ይወስዳል እንጂ፤ የጠየቀውን ያገኛል። በዚህ አኳኋን፤ አዶልፍ ማመልከቻውን ካቀረበ ከሁለት ዓመታት በኋላ፤ ግንቦት 5 ቀን 1927 ዓ.ም በጀርመን አገር ሙሉ የነዋሪነት ፈቃድ አገኘ። ስለዚህ፤ ይህ የኦስትሪያ ተወላጅ ከስድስት ዓመታት በፊት የመሰረተውን የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ፤ በይፋ አደባባይ ላይ አውጥቶ እንደፈለገው ትግሉን ማካሄድ የቻለው፤ በጀርመን አገር የመኖሪያውን ፈቃድ ካገኘ ወዲህ እንጂ፤ ከዚያ በፊት አልነበረም።

በጥቅምት 1922 ዓ.ም፤ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ጥቁር ሸሚዝ ለባሾቹን አሰልፎ ከሚላኖ እስከ ሮማ ያደረገውን ጉዞና፤ በፓርለማ ሥርዓት በሕግ የተቋቋመውን መንግሥት አስለቅቆ ሥልጣን እንዴት ለመያዝ እንደቻለ፤ አዶልፍ ሂትለር በዝርዝር ተከታትሎ ነበር። ነገር ግን፤ ምንም እንኳን ሙሶሊኒ የወሰደውን ደፋር የሆነ እርምጃና በመጨረሻም ሥልጣን በመያዝ ያገኘውን ውጤት አዶልፍ ከልቡ ቢያደንቅም፤ የዱቼን ዘዴ በጀርመን ሕዝብ ላይ ለመጠቀም የሚቻል ሆኖ አላገኘውም። የጣልያን ሕዝብ በተፈጥሮው የዋህና ድልል ስለሆነ፤ የፖለቲካ መሪዎቹ አነጋገሩን ካወቁበት፤ ምክራቸውን በቶሎ ተቀብሎ አብሯቸው ይሰለፋል። የጀርመን ሕዝብ ግን ከዚህ የተለየ ነው። ከፖለቲካ መሪዎች የሚቀርብለትን ሐሳብ ከመቀበሉ በፊት እጅግ አድርጎ ይመራመራል። የሚያምንበት ሆኖ ቢያገኘውም፤ በአደባባይ ተወዳድሮ በማሸነፍ እንጂ፤ ኃይልን ተመርኩዞ ሥልጣን መያዝን አይደግፍም። ስለዚህ፤ የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ ለአገር መሪነት ሥልጣን የሚበቃው፤ በዴሞክራሲ ሥርዓት የሕዝቡን ድጋፍ በማግኘት ስለሆነ፤ የትግላችን መሠረቱና መንገዱ ይህ ብቻ ነው በማለት፤ አዶልፍ ሂትለር ለማታለያ ያዘጋጀውን ጊዜያዊ የሆነ የዴሞክራት ልብሱን አጥልቆ ግሥጋሴውን ቀጠለ።

# ሂትለር ቻንስለር

በጀርመን አስተዳደር ወግ እስከዛሬ ድረስ የሚሠራበት "ቻንስለር" የተባለውን ማዕረግ ጠቅላይ ሚኒስትር ወይም የመንግሥት መሪ ማለት ነው። በብዙዎች የአውሮፓ አገሮች እንደሚታየው አሠራር፣ በጀርመን አገር የሬፑብሊኩ ፕሬዚዳንት የአገሩ መሪ ሲሆን፣ የፓርለማውን ድጋፍ ይዞ የመንግሥቱን ሥራ በሙሉ ሥልጣን የሚያካሂደው፣ ቻንስለሩ ነው።

አዶልፍ ሂትለር፣ የጀርመን ቻንስለር ለመሆን ከ1928 ዓ.ም እስከ 1933 ዓ.ም ድረስ፣ ለአምስት ዓመታት ያህል ያለማቋረጥ በብዙ ታግሏል። " ናሽናል ሶሲያሊስት " የተባለው የፖለቲካ ፓርቲው፣ ለፓርለማው የምርጫ ውድድር ለመጀመሪያ ጊዜ ሕዝብ ፊት የቀረበው ግንቦት 28 ቀን 1928 ዓ.ም ሲሆን፣ በዚያን ጊዜ ያገኘው ውጤት ሁለት ነጥብ ስድስት በመቶ (2.6%) ብቻ ነበር። እንደዚሁም፣ በዚያኑ ጊዜ ለፓርቲው አባል ለመሆን የተመዘገቡለት ደጋፊዎች፣ ቁጥራቸው ከአንድ መቶ ሰማንያ ሺህ የሚበልጡ አልነበሩም። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፣ የጀርመን ሕዝብ " ናሽናል ሶሲያሊስት " የተባለውን የፖለቲካ ፓርቲ ማወቅ የጀመረው፣ በ1929 ዓ.ም ለድል አድራጊዎቹ መንግሥታት ስለሚከፈለው የጦር ካሣ፣ አውን ያንግ (Owen Young) የተባለው አሜሪካዊ የፋይናንስ ኤክስፐርት ያቀረበውን ፕላን አጥብቆ በተቃወመ ጊዜ ነበር። ዋና ዋናዎቹ ናዚስቶች እነ ዮሴፍ ጉበል፣ የያንግ ፕላን እንኳንስ በእኛ ትውልድና ገና ባልተወለዱት የጀርመን ልጆች ላይ የሞት ፍርድ አዘጋጅቶ የሚጠብቅ ነው በማለት በነዙት ፕሮፓጋንዳ፣ ሕዝቡን በከፍተኛ የጋለ ስሜት ለመማረክ አስቻላቸው።

የናዚስቶቹ ተቃውሞ፣ በዚህ በጦር ካሣው አከፋፈል ጉዳይ ብቻ አልነበረም። ጦርነቱ ካለቀ በኋላ፣ በቬርሣይ ሸንጐ፣ ፈረንሣይና እንግሊዝ አሜሪካንን እና ጣልያንን ይዘው በጀርመን ላይ የፈረዱትን የግፍ ቅጣት፣ ሕዝቡ በትክክል እንዲያውቀው እየዘረዘሩ በማስረዳት ነበር። ይኸውም:-

- የጀርመን ሕዝብ በአውሮፓ ያሉትን ስልሣ ስምንት ሺህ እስኪር ኪሎ ሜትር ስፋት ያላቸውን ግዛቶቹን ተነጥቋል። ከዚህም ጋር በነዚህ ግዛቶቹ ላይ ነዋሪዎች የሆኑት ስምንት ሚሊዮን ወንድሞቹና እህቶቹ ተገንጥለው ለሌሎች ገዥዎች እንዲሰጡ ተደርጓል።

- በአፍሪካና በእስያ የነበሩት ቅኝ ግዛቶቹ፣ ለፈረንሣይና ለእንግሊዝ ጥቅም እንዲውሉ ተደልድለዋል።

- አዲስ የተቋቋመው የጀርመን ሬፑብሊክ መንግሥት፣ የፈረንሣይና የእንግሊዝ ባለሥልጣኖች ተወራጅ ሆኖ እንዲኖር ስለተወሰነበት፣ ያለ እነሱ ፈቃድ የአገር መከላከያ ድርጅት አይኖረውም።

- ያለ እነሱ ፈቃድ የጦር መሣሪያ ፋብሪካዎች ማቋቋም አይችልም።

- ያለ እነሱ ቸርነት እንደ ራይንላንድ (Rhine Land) የመሳሰሉትን የራሱን ግዛቶች መቆጣጠርና ማስተዳደር አይፈቀድለትም።

በጠቅላላው የጀርመን መንግሥት ነፃነት የሌለውና ምንም ዓይነት የዕድገት እርምጃ ለማድረግ እንዳይችል፣ በፈረንሣይና በእንግሊዝ ሥልጣን ተወጥሮ የተያዘ ከመሆኑም በላይ፣ ይህ ሕዝብ እንጀቱን አስሮ በጦር ካሣ ስም ዕዳ እየገበረ ዕድሜውን እንዲጨርስ ተፈርዶበታል። ስለዚህ፣ የጀርመን ሕዝብ የወደቀበትን ይህን ሁሉ ስቃይ ተጋፍጦ የሚታገልለትና በመጨረሻም አሸንፎ ነፃነቱን የሚመልስለት፣ ከዚያም አልፎ አለአግባብ ከሕግ ውጭ የተፈረደበትን የግፍ እዳ የሚሰርዝለት፣ ጠንካራ መሪና ብድር መላሽ አስተዳዳሪ ያስፈልገዋል። ለዚህም ቆራጡ መሪያችን አዶልፍ ሂትለርና መስረታዊው መመሪያችን የሆነው የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲያን ተደራጅተዋል ... በማለት፣ ናዚስቶቹ ሲነዙት የቆዩት ፕሮፓጋንዳ በመጨረሻው ከሚፈልጉት ግብ ለመድረስ አብቅቷቸዋል።

በዚህ አኳኋን፣ በግንቦት 1928 ዓ.ም በተደረገው የፓርለማ አባሎች ምርጫ፣ ሁለት ነጥብ ከስድስት በመቶ (2.6%) ብቻ ውጤት ያገኘው የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ፣ በየጊዜው በሕዝብ ዘንድ ታዋቂ እየሆነ፣ ከአራት ዓመታት በኋላ ሐምሌ 31 ቀን 1932 ዓ.ም በተካሄደው ጠቅላላ ውድድር፣ ሰላሣ ሰባት ነጥብ ሦስት በመቶ (37.3%) በማምጣት፣ ከልዩ ልዩ ፓርቲዎች ሁሉ የበላይነትን አገኘ። በዚህ ጊዜ የሬፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ማርሻል ሂንደንቡርግ፣ (Hindenburg) ከአምስት ወራት በፊት በአፌሲየር የጀርመን ዜግነቱ የፀደቀለትን ሂትለርን ጠርቶ ካቢኔውን እንዲያቋቁም መጠየቅ ነበረበት። ነገር ግን፣ ሂንደንቡርግ ከቀድሞዎቹ የዳግማዊ ጊዮም ጄኔራሎች አንዱ የነበረ በመሆኑ፣ በጦርነቱ ጊዜ የደረሰውን የአምሳ አለቃ ሂትለርን ታሪክ በማስታወስ፣ " ... ቻንስለር መሆን የሚገባው አይደለም። ከናዚስቶቹ መካከል ሌላ ሰው ተመርጦ ካቢኔውን ያቋቁምና ለአዶልፍ ቢበዛ የፖስታ ሚኒስትርነቱ ቢሰጠው ይሻላል ... " የሚል አስተያየት ሰጠ። የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ አባሎች ግን፣ የፕሬዚዳንቱን ሐሳብ ጨርሶ አንቀበልም አሉ። " ... በውድድሩ አሸናፊዎች ሆነን ትልቁ ፓርቲ የኛ ናሽናል ሶሲያሊስት ሆኗል። በዚህ መሠረት የቻንስለርነቱ ቦታ የኛ ነው። መሪያችንም አዶልፍ ሂትለር ነው። ሌላ አናውቅም ... " ብለው አቋማቸውን አጠነከሩ። የሬፑብሊኩ ፕሬዚዳንት የራሱን ሐሳብ ለማስፈጸም ለጥቂት ወራት ሲያንገራግር ከቆየ በኋላ፣ በመጨረሻው አዶልፍ ሂትለርን ጠርቶ አዲሱን ካቢኔ እንዲያቋቁም በመጠየቅ የቻንስለርነቱን ሹመት መስጠት ግዴታ ሆነበት።

እንግዲህ ! የኦስትሪያው ተወላጅ አዶልፍ ሂትለር፣ በየካቲት 25 ቀን 1932 ዓ.ም የጀርመንን ዜግነት አግኝቶ፣ ፓስፖርቱን ከተቀበለ ከአሥራ አንድ ወራት በኋላ፣ በዚህ በጥር 30 ቀን 1933 ዓ.ም " ቻንስለር " ተብሎ መንግሥቱን የመምራት ሥልጣን ተቀበለ። እስካሁን ድረስ፣ እዚህ ደረጃ ለመድረስ አዶልፍ ያደረገውን ትግልና የተጓዘባቸውን ጉዳናዎች ከብዙ በጥቂቱ ለማሳየት ሞክረናል። በሚቀጥለው ምዕራፍ ደግሞ ሥልጣን ከጨበጠ በኋላ፣ የተከተለው አሠራርና የወሰዳቸው እርምጃዎች በዓለም ላይ ምን እንዳስከተሉ እናያለን።

# ምዕራፍ ፪

## ሥልጣን በሂትለር እጅ ብቻ

ከዚህ በፊት በቀረበው ምዕራፍ ላይ እንደ ተገለጸው፤ አዶልፍ ሂትለር የጀርመን መንግሥት መሪ ለመሆን የቻንስለርነቱን ሹመት የተቀበለው፤ በዴሞክራሲ ሥርዓት በአገሩ ውስጥ በተደረገው ምርጫ፤ የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲው ከሌሎቹ የፖለቲካ ፓርቲዎች ሁሉ ብልጫ ያገኘ በመሆኑ ነው። እንደሚታወሰው፤ በተለይ ከ1928 ዓ.ም ጀምሮ ሂትለርና ቡድኑ፤ ለአራት ዓመታት ባለማቋረጥ የፖለቲካ ትግል በሚያደርጉበት ጊዜ፤ የአገሩን የመሪነት ሥልጣን ለመያዝ የተጓዙት የዴሞክራሲን ጉዳና እንደሚከተሉ በማስመሰል እንጂ፤ ኃይልን በመመርኮዝና ሕዝብን በማሸበር አለመሆኑን አስመስክረዋል። ይህ "ናሽናል ሶሲያሊስት" የተባለው የፖለቲካ ፓርቲ ዓላማውና ግቡ፤ የጀርመንን ሕዝብ ከመከራው ዓለም ለማላቀቅና፤ ለአገር ትልቅነትና ክብር ለመዋጋት መሆኑን በሚማርክ ፕሮፓጋንዳ፤ ናዚስቶቹ እየተነተኑ በሚያስረዱበት ጊዜ፤ ድጋፉን የለገሳቸው አብዛኛው የጀርመን ሕዝብ፤ ሥልጣን ሲጨብጡ ወደ ክፉ አቅጣጫ ሊያመሩ ይችላሉ ብሎ አልተጠራጠራቸውም ነበር።

ትልቁ ጉድ የፈላው፤ ጥር 30 ቀን 1933 ዓ.ም ሂትለር የቻንስለርነቱን ሥልጣን በተቀበለ ማግሥት፤ ለጀርመን ሕዝብ ክብርና ለአገሩ ትልቅነት፤ እፈጽማቸዋለሁ ብሎ ያዘጋጃቸውን ፕሮግራሞች ሲያስታውቅ ነው። ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ መላው የጀርመን ሕዝብ የሂትለርን ፕሮፓጋንዳ ሲያዳምጥ የኖረው፤ ጠላቶቹ የሆኑት የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት ከጣሉበት ቀንበር በምን አኳኋን እንደሚላቀቅና ትክክለኛ የሆነ መብቱን አግኝቶ ወደ ብልጽግና ሕይወት ለማምራት እንዴት እንደሚሸጋገር ነበር። ነገር ግን፤ ከዚህ ትልቅ ተስፋ ከሚሰጥ ሐሳብ ጋር ተጣምሮ የተዘጋጀውን የጨካኝ ዲክታተርነት አመራርና ከሰብአዊ መንፈስ ውጭ ለመፈጸም ያቀደውን የዘረኛነት ፖሊሲ፤ ሕዝቡ የሚጠብቀው አልነበረም። ይሁን እንጂ፤ አዶልፍ ሂትለር Main Kampf " የእኔ ትግል" በሚለው የፍልስፍና መጽሐፉ ውስጥ፤ የአገሩን ሥልጣን ከተቀበለ በኋላ በየደረጃው ለመፈጸም ያሰባቸውን እጅግ አደገኛ የሆኑትን ሐሳቦቹን ሁሉ ዘርዝሮ ከማስረዳት አልተቆጠበም ነበር።

ከሁሉ አስቀድሞ ሂትለር ፍጹም ዘረኛ መሆኑን አልደበቀም። የሰው ልጅ ዘር ሁሉ እኩል እንዳልሆነና የጀርመን ሕዝብ ደግሞ ከሌላው ሁሉ የበላይነት ያለው መሆኑን አጥብቆ እንደሚያምንበት አስረድቷል። ስለዚህም ጉዳይ ሲያብራራ፤ የጀርመን ሕዝብ " አርየን (Aryenne) ከተባለው ንጹሕ የነጭ ዘር የመጣ ሲሆን፤ ከጊዜ በኋላ ከሌሎቹ ዝቅተኞች ከሆኑት ከአይሁዳውያንና ከሴምያውያን (ሰሚቲክ) ዘሮች ጋር በመቀላቀል ዘር ሲበላሽ በመቆየቱ፤ እጅግ አድርጉ የሚቆጨው መሆኑን በምሬት ገልጿል። ለዚህም መፍትሔውን በጽሑፉ ላይ እንደ አመለከተው፤ ከእንግዲህ ወዲህ ይህ ከአሪየን ሲያያዝ የመጣው ዘር፤ እየተጣራ በሚገባ ለመስፋፋት እንዲችልና የጀርመን ሕዝብ ቀድሞ በዓለም ላይ የነበረውን

የዘር የበላይነት ደረጃ እንዲያገኝ፣ የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲ ዋና ዓላማ መሆኑን ያረጋግጣል።

እንግዲህ ! ይህ ፍጹም ዘረኛ የሆነ ዲክታተር ሥልጣን ከያዘ በኋላ፣ የሚያስበውን በተግባር ለማዋል የሚወስደው እርምጃ ሁሉ ያለ አንዳች ርኅራኄና ይሉኝታ መሆኑን በሚገባ አስረድቷል። በመጀመሪያ ደረጃ ከሚፈጸሙትም ዋና ዋና ጉዳዮች፣ የአይሁዳውያንን እና የሲምያውያንን ተወላጆች የማምከኛ መርፌ በግዴታ በማስወጋት፣ ዘራቸው ከንጹሑ ከጀርመን ደም ጋር እንዳይቀላቀል ማድረግ ነበር። በሁለተኛ ደረጃ ደግሞ፣ በተለይ በብዙ ሚሊዮን የሚቆጠሩት አይሁዳውያኖች እየተለቀሙ፣ ወደ ልዩ መስፈሪያ ቦታ እየተወሰዱ የስቃይ ሕይወት ሲቀበሉ ከከረሙ በኋላ፣ በጋዝ መርዝ እየታፈኑና እየተቃጠሉ እንዲያልቁ መደረጋቸው ይታወሳል። በዚህ ረገድ ዘረኛው ሂትለር በሰው ልጆች ላይ የፈጸመውን የጭካኔ ሥራ በየዓይነቱ ዘርዝሮ ለመግለጽ፣ ራሱን የቻለ መጽሐፍ ከማዘጋጀት በስተቀር፣ ከሌላ ታሪክ ጋር አጣምሮ ለማስረዳት ቀላል አይሆንም።

እ.ኤ.አ ሐምሌ 31 ቀን 1932 ዓ.ም በመላ ጀርመን በተደረገው ጠቅላላ የፓርላማ ምርጫ፣ የሂትለር ቡድን ሰላሳ ሰባት ነጥብ ሦስት በመቶ (37. 3%) በማግኘት ከሌሎቹ የፖለቲካ ፓርቲዎች ሁሉ ብልጫ ስለአመጣ፣ ወዲያውኑ የመንግሥቱን መሪነት ሥልጣን ሊሰጠው ይገባ ነበር። ነገር ግን፣ የጀርመን ሬፑብሊክ ፕሬዚዳንት ማርሻል ሂንደንቡርግ ይህን የቀድሞ የአምሳ አለቃ፣ ቻንስለር ማድረግ ተገቢ አይደለም በማለት ለብዙ ወራት ሲያንገራግር ከቆየ በኋላ፣ በመጨረሻው ሳይወድ በግዴታ ጥር 30 ቀን 1933 ዓ.ም እኩለ ቀን ላይ ሂትለርን ጠርቶ መንግሥት እንዲያቋቁም መጠየቁ ይታወሳል። አዶልፍ፣ ከዐሥር ዓመታት በላይ ሲመኘውና ሲለፋበት የኖረውን ይህንን የመንግሥት መሪነት ሥልጣን በተቀበለ ማግሥት ሳይውል ሳያድር፣ ፕሬዚዳንት ሂንደንቡርግን አስጨንቆ በሚቀጥሉት ሰላሳ ቀናት ውስጥ አሁን ያለው ፓርለማ ተበትኖ ሌላ አዲስ ጠቅላላ ምርጫ እንዲከናወን አስወሰነ። ይህ ምርጫ እንዲደረግ ሂትለር የፈለገው፣ የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲው ካለፈው የበለጠ የሕዝብ የድጋፍ ድምፅና የፓርለማ ወንበር በማግኘት፣ ተወዳዳሪ የሌለው መሪ ለመሆን ነበር። ፊዩረር ሂትለር፣ እንደ ተመኘው ቻንስለርነቱን ከተቀበለ ከሁለት ወራት በኋላ በተደረገው ጠቅላላ ምርጫ፣ የናሽናል ሶሲያሊስት ፓርቲው ቀድሞ ከነበረው ከሠላሳ ሰባት ነጥብ ሦስት (37.3%) ወደ ዐርባ ሦስት ነጥብ ዘጠኝ ( 43.9%) ከፍ በማለት የዐሥራ ሰባት ሚሊዮን (17.000,000) ሕዝብ ድጋፍ ስለአገኘ፣ ወዲያውኑ በሥልጣኑ የሚከተሉትን እርምጃዎች ወሰደ።

1) መጋቢት 20 ቀን 1933 ዓ.ም የአዶልፍ ሂትለር መንግሥት "ሦስተኛው የጀርመን ዳይናስቲ" ተብሎ እንዲሠየም አወጀ። (THIRD REICH)

2) ሚያዝያ ሰባት ቀን 1933 ዓ.ም ሂትለር ባወጣው አዲስ ሕግ፣ ከጀርመን ሕዝብ ጋር እየተዋለዱ ዘር ሲያረክሱ የኖሩ ናቸው በመባል የተወነጀሉት አይሁዳውያንና ሌሎቹም ጥቁሮች፣

ሀ) እያንዳንዳቸው የማምከኛ መድኃኒት በመርፌ እንዲወጉ አደረገ።

ለ) በመንግሥት ሥራና በመምህርነት የሚያገለግሉት አይሁዳውያን ከየሥራ ገበታቸው በፍጥነት እንዲባረሩ ትዕዛዝ ሰጠ።

ሐ) በንግድ ሥራ የተሠማሩት አይሁዳውያኖች ደግሞ፤ ድርጅቶቻቸውና ሱቆቻቸው በወታደር ኃይል እንዲወድሙ ወሰነ።

3) ጥቅምት 14 ቀን 1933 ዓ.ም የጀርመን መንግሥት አባል ከሆነበት ከሊግ ኦፍ ኔሽን ለቅቆ እንዲወጣ በይፋ አስታወቀ።

4) ነሐሴ 2 ቀን 1934 ዓ.ም የሬፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ማርሻል ሂንደንቡርግ በተወለደ በ87 ዓመቱ ሲሞት፤ ለሂትለር አንድ ተጨማሪ የሥልጣን ማስፋፊያ ዕድል ከፈተለት። ሂንደንቡርግ በሞተ በሁለተኛው ቀን፤ ከእንግዲህ ወዲህ የአገሩ ፕሬዚዳንትና የመንግሥቱ መሪ (ቻንስለር) አንድ ሰው ብቻ መሆን ይችላል የሚል ሕግ አዘጋጅቶ፤ ነሐሴ 19 ቀን 1934 ዓ.ም የሕዝብ ውሳኔ (Plebiscite) እንዲሰጥበት ጠየቀ። ከሕዝቡም መካከል ዘጠና በመቶው የቀረበለትን የፊዩረርን ጥያቄ ስለደገፈ፤ ከዚህ ዕለት ጀምሮ አዶልፍ ሂትለር ለመላው የጀርመን ሕዝብ ወሰን የሌለው ባለሙሉ ሥልጣን መሪ እኔ ብቻ ነኝ አለ። ለዚህም፤ እንደ ጣኦት ልዩ አምልኮት እንዲሰጠው ያወጣው መፈክር፤ " ... አንድ አገር ... አንድ ዘር ... አንድ ዳይናስቲ ... አንድ መሪ ... " * የሚል ሲሆን፤ ይህንን ሁሉ ጠቅሎ የሚጎናጸፈው መሪ፤ ፊዩረር ሂትለር ብቻ መሆኑን ያለ አንዳች ይሉኝታ ሕዝቡ በደስታ እንዲፈጽም ተነገረው።

ሥልጣን ለመያዝ የዴሞክራሲን መንገድ ተከትሎ በማሸነፍ እንጂ፤ ኃይልን በመጠቀም መሆን የለበትም እያለ በማታለል የሚፈልገውን ካገኘ በኋላ፤ አዶልፍ ሂትለር እስከ ዕድሜ ልኩ በዘረጋው ፕሮግራም፤ የጀርመንን ሕዝብ የሚመራው፤ እሱ እንደሚፈልገው በራሱ ዕምነትና በራሱ ውሳኔ ብቻ ስለሆነ፤ የዴሞክራሲ ወጉም ሆነ ሥርዓቱ፤ ሳይውል ሳያድር በፍጥነት እንዲቀበር አደረገ። በአገሩ ውስጥ ከነበሩት የፖለቲካ ፓርቲዎችም ውስጥ፤ ከናዚስቶቹ በስተቀር ሌሎቹ በሙሉ መፍረስ ብቻ ሳይሆን መጥፋትም አለባቸው ብሎ ፈረደባቸው። ፊዩረር ሂትለር፤ ለጀርመኖች ያለመላቸው ግብ፤ ዘራቸው ብቻ ሳይሆን ታሪካቸውም ጭምር ከሁሉም በላይ መሆኑን የዓለም ሕዝብ በግዴታ እንዲቀበለው ለማድረግ ነው። ፊዩረር ሂትለር ይህን ዓላማውን ከግቡ ለማድረስ የሚችለው፤ በተቻለ ፍጥነት የጦር ኃይሉን በማስፋፋትና ጠላቶቼ ከሚላቸው ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ አገሮች የበለጠ በማድረግ ስለሆነ፤ **በመጀመሪያ የወሰዳቸው እርምጃዎች በቬርሣይ ውል በጀርመን ላይ የተወሰኑትን የቅጣት ደንቦች ሁሉ አንድ በአንድ በማፍረስ ነበር።**

ቀደም ሲል እንደ ተጠቀሰው፤ አዶልፍ ሥልጣን በያዘ በዐሥረኛው ወር (በጥቅምት 1933) ጀርመን ከሊግ ኦፍ ኔሽን አባልነቷ እንድትወጣ ካደረገ በኋላ፤ በመጋቢት 16 ቀን 1935 ዓ.ም በቬርሣይ ውል የተከለከለውን ሁሉ በመጣስ፤ ከፍ ያለ የጦር ኃይል ለማቋቋም መወሰኑን በይፋ አስታወቀ። ይህን አስደንጋጭ የሆነ የማይጠበቅ መግለጫ ከማውጣቱ በፊት፤ ሦስት መቶ ሺህ (300.000) ያገር መከላከያ ወታደሮች ለማቋቋም የፈረንሣይ መንግሥት እንዲፈቅድለት፤ በአምባሳደሩ በፍራንስዋ ፖንሴ በኩል ያቀረበውን ልመና፤ የፓሪስ መንግሥት

* (une seule nation, un seul empire, un seul chef)



አዶልፍ ሂትለር እ.ኤ.አ ጥር 30 ቀን 1933 ዓ.ም በዚህ ናዚስታዊ በሆነ ሰላምታው፤ የመላው ጀርመንን አስተዳደር ሥልጣን ተረከበ፤

ባለሥልጣኖች ሳይቀበሉት ቀርተው ነበር። እንደሚታወቀው፣ የቬርሣይ ውል የሚፈቅድለት፣ ከአንድ መቶ ሺህ የማይበልጡ ወታደሮች እንደዲኖሩት ብቻ ነው። ነገር ግን፣ ፊዩረሩ በሰላምና በዲፕሎማሲ ጉዳና የወታደሮቹን ቁጥር ወደ ሦስት መቶ ሺህ ከፍ ለማድረግ ያቀረበውን ጥያቄ ሲከለክሉት፣ እጅሬ በገዛ ሥልጣኑ በሠላሳ ስድስት (36) ዲቪዚዮን የተደራጀ የአምስት መቶ ሺህ (500.000) የጦር ኃይል ወታደሮች መልምሎ ማቋቋሙን አስታወቃቸው።

የሂትለር ሕገወጥ ውሳኔ እንደ ተሰማ፣ በፓሪስ የፖለቲካ አደባባይ ላይ ትልቅ የብስጭት ቦንብ ፈነዳ። የልዩ ልዩ የፖለቲካ ፓርቲዎች ሁሉ የጀርመኑ ዲክታተር የወሰደውን እርምጃ በማውገዝ፣ ከመንግሥታቸው ጋር ተባበሩ። የታላቋ ብሪታንያ ጠቅላይ ሚኒስትርም፣ እንደ ፈረንሣይ የጋለ ባይሆንም በእንግሊዝ ሕዝብ ስም ሆኖ ተቃውሞውን አሰማ። የጣልያኑ ዱቼ ሙሶሊኒ፣ በዚያን ዓመት (1935 ዓ.ም) ኢትዮጵያን በጦር ለመውጋት በመዘጋጀት ላይ ስለነበረ፣ የፈረንሣይንና የእንግሊዝን መንግሥታት ወገኖቹ ለማድረግ፣ የሂትለር ሕገወጥ እርምጃ የአውሮፓን ሰላም የሚነሣ ነው ብሎ ፎከረ። ከዚህም አያይዞ ሦስቱ የአውሮፓ ታላላቅ አገሮች በፋሽስታዊት ጣልያን ጋባዥነት፣ ስትሬሳ (Stresa) በተባለችው በጣልያን ሰሜናዊ ከተማ ልዩ ስብሰባ አድርገው፣ አንድ ዓይነት እርምጃ እንዲወስዱ ጋበዘ። ዱቼ ባቀረበው ሐሳብ መሠረት፣ ሂትለር የቬርሣይን ውል መጣሱን ባስታወቀ በሦስተኛው ሳምንት፣ ከሚያዝያ 11 እስከ 14 1935 ዓ.ም ድረስ፣ የእንግሊዝ ጠቅላይ ሚኒስትር ማክዶናልድና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ጆን ሲሞን፣ የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር ፍላንደን እና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ላቫል፣ በሙሶሊኒ ሊቀመንበርነት ተሰብስበው፣ ናዚስቱ ዲክታተር ስለወሰደው ሕገወጥ እርምጃ በሰፊው ተወያዩ።

የዚህ የስትሬሳ ስብሰባ ሲወጠንና ሲዘጋጅ፣ በመላው የአውሮፓ አገሮች ዘንድ ያሳደረው ስሜት፣ ያለ ጥርጥር ፈረንሣይና እንግሊዝ ጣልያንንም ጨምረው ጦር በማንሣት፣ ዲክታተሩ ያቀደውን እንዲሰርዝ ያስገድዱታል የሚል ነበር። ሂትለርም የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት በጀርመን ላይ ጦር ከማንሣት አይመለሱም ይሆናል የሚል ሥጋት እንደነበረው ታውቋል። ነገር ግን፣ እነዚህ ሦስቱ የአውሮፓ ታላላቅ መንግሥታት ስትሬሳ ደርሰው ስብሰባቸውን ሲጀምሩ፣ በናዚስቱ ዲክታተር ላይ ስለሚወስዱት እርምጃ እያንዳንዳቸው የተጨበጠ ሐሳብ አልነበራቸውም። በተሰበሰቡበት ገበታ ዙሪያ ላይ ሐሳብ ለሐሳብ ሲለዋወጡ፣ የሂትለር መንግሥት የቬርሣይን ውል እንዲያከብር ለማስገደድ የሚያስችል ኃይል በዚያን ሰዓት እንዳልነበራቸውና እንዳልተዘጋጁ በትክክል ለመረዳት ቻሉ። የስብሰባው ሊቀመንበር ቤኒቶ ሙሶሊኒም፣ ውስጥ ውስጡን የሂትለር ደጋፊ ስለሆነ፣ በአሁኑ ሰዓት በጀርመን ላይ ጦርነት መክፈት የሚፈለገውን ከማግኘት ይልቅ፣ ብዙ ጣጣ ማስከተሉ የሚያመዝን መስሎ ስለሚታይ፣ ሂትለር የቬርሣይን ውል በመጣስ እስከ አሁን የፈጸመውን በጥብቅ አውግዘን፣ ለወደፊቱ በዚህ የማይገታ ከሆነ፣ የኃይል እርምጃ እንድንወስድበት መዘጋጀት ይሻላል፣ የሚል ሐሳብ አቀረበ። እንደሚታየው የዱቼ አስተያየት ይህን ያህል የሚያጠግብ አልነበረም። ከቬርሣይ ውሎች ውስጥ ፈረንሣይና እንግሊዝ በጣም የሚተማመኑበት፣ ጀርመን ለምን ጊዜውም የአጥቂ ጦር ኃይል እንዳይኖራት የተደረገባትን ውሳኔ ነበር። አሁን ሂትለር በማን አለብኝ መንፈስ ይህንን ውል ጥሶ የሚፈልገውን ካደረገ፣ ሌሎቹና ቀሪዎቹ የቬርሣይ ውሎች ይህን ያህል የሚከብዱና ዋስትና የሚሰጡ አለመሆናቸው ለማንም ግልጽ ነው። ሙሶሊኒ ይህንን የተዳከመ

ሐሳብ ያቀረበው፤ የፈረንሣይንና የእንግሊዝን ለአጥቂነት አለመዘጋጀት በማየት ነው። በመጨረሻው እንደታየው፤ የስትሬሳ ኮንፌራንስ ሲፈጸም የሰጠው ውጤት፤ በጦር ድርጅትና በመሣሪያ ትጥቅ ረገድ፤ ትልቁን የቬርሣይን ውል ያፈረሰውን ዲክታተር በብርቱ ከማውገዝና ለወደፊቱ ከማስጠንቀቅ በስተቀር፤ የኃይል እርምጃ ለመውሰድ ያልታሰበ ስለሆነ፤ ፉዩረር ሂትለር ትልቅ ድል እንዳገኘ አድርጐ በመቁጠር ተደስቶበታል።

ብዙዎቹ የታሪክ ጸሐፊዎች እንዳመለከቱት፤ ሂትለር ከፉኛ የልብ ልብ የተሰማው፤ ፈረንሣይና እንግሊዝ በሙሶሊኒ ሊቀመንበርነት በስትሬሳ ከተማ ካደረጉት ስብሰባ በኋላ ነው። በእውነቱ ሂትለር የወሰደውን ሕገ ወጥ እርምጃ እንዲሰርዝ ለማድረግ፤ ፈረንሣይና እንግሊዝ ቆራጦች ቢሆኑ ኖሮ፤ በዚያን ጊዜ የነበራቸው የጦር ኃይል አያንሳቸውም ነበር። ሂትለርም ይህንን የቬርሣይን ውል ማፍረሱን ሲያስታውቅ፤ ከፍ ካለ የሥጋት ስሜት ጋር ስለሆነ፤ ጦር እናነሣብሃለን ቢሉት ኖሮ፤ ለመመከት የሚያስችል አቅም አልነበረውም። ነገር ግን፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት፤ በሂትለር ጉዳይ የጠነከረ አንድነት ስለሌላቸው፤ የስትሬሳ ኮንፌራንስ ውጤቱ ባዶ ሆነ። ከዚህ በላይ ደግሞ እጅግ አስገራሚ የሆነው፤ የስትሬሳ ስብሰባ ከተካሄደ ከሦስት ወራት በኋላ፤ ጀርመን የባሕር ኃይል ለማቋቋም እንዲችል፤ የእንግሊዝ መንግሥት ፈቃደኛ ሆኖ ከሂትለር ጋር ስምምነት መፈራረሙ ነው። እንግዲህ እዚህ ላይ ፈረንሣይ ብቻዋን በንዴት ብትቃጠል ምን ውጤት ታመጣለች? .... ሂትለርም የሁለቱ የዴሞክራሲ መንግሥታት በአንድ አቋም ላይ አለመገኘት በጣም ስለተመቸው፤ ከዐሥራ ስድስት ዓመታት በፊት የተፈረመውን የቬርሣይን ውል አንድ በአንድ እየጣሰ፤ የጦር ኃይሉን እያስፋፋ ለመንዝ መንገዱ ከፍት ሆነለት።

# ምዕራፍ ፲

## የሙሶሊኒ እና የሂትለር መቀራረብ

በእነዚህ በሁለቱ ዲክታተሮች መካከል፣ የዕድሜ የኤክስፒሪያንስና የጠባይ ልዩነት አለ። ሙሶሊኒ ሂትለርን በዕድሜ ስድስት ዓመት ይበልጠዋል። በአገር መሪነትም ሙሶሊኒ ከሂትለር በዐሥራ አንድ ዓመታት ከፍ ይላል። በጠባይ ረገድም፣ ሂትለር በቆራጥነትና በፍጹም ጨካኝነት የታወቀ ሲሆን፣ ሙሶሊኒ ልበ ፈሪና ወላዋይ መሆኑ በሰፊው ይነገርለታል። በመሠረቱ፣ ሁለቱ ሰዎች የሚቀራረቡት በሁለት ዋና ዋና ጉዳዮች ላይ ብቻ እንደነበረ ታይቷል። ይኸውም፣ የመጀመሪያው፣ ሁለቱም ፍጹም ዲክታተሮች ሲሆኑ፣ ሁለተኛው ደግሞ፣ ሁለቱም ፀረ ኮሙኒስቶች መሆናቸው ነው። ከዚህ በቀር ደግሞ፣ ሙሶሊኒ ሥልጣን ላይ የወጣው፣ በኩዴታ መልክ የፋሽስት ሚሊሻዎቹን አዘጋጅቶ፣ በቦታው ላይ የነበረውን በሕዝብ የተመረጠ መንግሥት በኃይል በማስገደድ ሲሆን፣ ሂትለር ደግሞ በዴሞክራሲ ሥርዓት ተወዳድሮ የሕዝብ ድጋፍ በማግኘት ነው። ፊዩረር ሥልጣን ከያዘ በኋላ፣ የዴሞክራሲን ሥርዓት ለመቅበር የወራት ጊዜ አልወሰደበትም። ሙሶሊኒ ግን፣ ሥልጣን ለመያዝ ትግሉን ያካሄደው በሬቮሉሽን መልክ ስለሆነ፣ የዲክታተርነትን አስተዳደር የመሠረተው ገና ከጠዋቱ ነው።

እ.ኤ.አ በ1933 ዓ.ም አዶልፍ ሂትለር የተመረጠበትን የዴሞክራሲውን ሥርዓት አፍርሶ፣ ሙሉ ዲክታተር መሆኑን ሲያውጅ፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ከመሰል ጓደኛው ጋር ከማጨብጨብ ይልቅ፣ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ መንግሥታት ጋር ሆኖ ሂትለርን እየነቀፈ መቆየትን መርጦ ነበር። በዚህ አኳኋን ሁለቱ የጣልያንና የጀርመን ዲክታተሮች አንዱ አንደኛውን በመጠራጠር ለሦስት ዓመታት የሞቀ የወዳጅነት ግንኙነት ሳይዘረጉ ቆይተዋል። ፈረንሣይና እንግሊዝም ይህ ሁኔታ የሚዘልቅ መስሏቸው፣ ከሙሶሊኒ ጋር ወዳጅነትን እያፋፋሙና ሂትለርን በጥላቻ መንፈስ እያራቁ ለማቆየት ብዙ ጥረት አድርገው ነበር።

ሙሶሊኒ የሴቷ ልጁ ባለቤት የሆነውን ወጣቱን ጋሌአሶ ቺያኖን (Galeazzo Ciano) በ1936 ዓ.ም መጀመሪያ ላይ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አድርጎ ሲሾመው፣ በጀርመንና በጣልያን ዲክታተሮች መካከል አዲስ የወዳጅነት ግንኙነት ተከፈተ። ኮምት ቺያኖ (Comte Ciano) የዱቼ አማች ከመሆኑም በላይ፣ ወራሹ ይሆናል እየተባለ ከፍ ያለ ግምት የተሰጠው ስለሆነ፣ የፋሽስቱን መንግሥት የውጭ ጉዳይ ፖሊሲ የሚመራው በሙሉ ሥልጣን መሆኑ ታወቀ። የመጀመሪያ እርምጃውም ሙሶሊኒንና ሂትለርን ማወዳጀት ነበር። እንደሚታወሰው፣ በ1935 ዓ.ም ሂትለር የኢትዮጵያን በፋሽስት መያዝ አልደገፈም። ይኸውም፣ ለኢትዮጵያ አዝኖ ሳይሆን የሙሶሊኒን በአፍሪካ መስፋፋት ባለመደገፍ መሆኑ የታወቀ ነው። ፊዩረር ለኢትዮጵያ አርበኞች በአንድ ዓይነት ዘዴ የጦር መሣሪያ ለማቀበል ያደረገው ሙከራ ሁሉ፣ ከእንግሊዞችና ከፈረንሣዮች ቁጥጥር የተነሣ ባለመሳካቱ፣ አዝኖ እንደነበረ ይነገራል። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም እ.ኤ.አ በ1956 ዓ.ም ሴርጅ ግሩሳርድ (Serge Groussard) ለተባለው የፈረንሣይ ፊጋሮ (Figaro) ጋዜጠኛ በሰጡት ኢንተርቪዩ፣

የሂትለር ጀርመን ኢትዮጵያን በጦር መሣሪያ ለመርዳት ያደረገውን ሙከራ መግለጻቸው ይታወሳል። በ1935 ዓ.ም ሙሶሊኒም በዚህ ቅር የተሰኘ ስለነበረ፣ ከሂትለር ጋር ወዳጅነትን ለመዘርጋት አልተጣደፈም።

ጥቅምት 24 ቀን 1936 ዓ.ም ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን በያዘ በአምስተኛው ወር፣ የዱቼ አዲሱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ጋሌአሶ ቺያኖ (Galeazzo Ciano) ለመጀመሪያ ጊዜ ጀርመንን ሲጐበኝ፣ ሂትለርንና ሙሶሊኒን ለማቀራረብ የሚያስችል አዲስ በር ከፈተ። በርቸትስጋድን (Berchtes Gaden) በተባለው ቤተመንግሥቱ ፊዩረር ሂትለር የፋሽስቱን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ለመጀመሪያ ጊዜ ሲቀበል፣ የሙሶሊኒ አማች ያቀረበለት ገጸ በረከት የናዚስቶቹን መሪ እጅግ የሚያስደስት ሆነ። ይኸውም፣ በእንግሊዝ አገር የሙሶሊኒ አምባሳደር የሆነው ዲኖ ግራንዲ (Dino Grandi) በገንዘብ አሰርቆ ያገኘውን፣ የታላቋ ብሪታንያ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን፣ " የናዚስቶች አደገኛነት " በሚል ርዕስ ያዘጋጀውን የምሥጢር ዶክመንት ነበር። ይህም ዶክመንት፣ የሂትለር መንግሥት የአውሮፓን ሰላም ለማናጋት የሚዘጋጀው፣ በምን መልክ እንደሆነና ለዚህም መከላከያው ምን እንደሚሻል የሚተነትን ስለሆነ፣ ፊዩረር ከመጠን በላይ ተደሰተ። ሂትለር፣ ከፋሽስቱ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ጋር ባደረገው ሁለት ሰዓት በፈጀው የሐሳብ መለዋወጥ ውስጥ፣ " .... **ዱቼ ከዓለም መሪዎች መካከል የመጀመሪያው ታላቅ ሰው በመሆኑ፣ ማንም ሰው ከእሱ ጋር እንኳንስ በቅርብ፣ በሩቅም ቢሆን ለመመሳሰል የመሞከር መብት የለውም** .... " ሲል፣ ፊዩረር የገለጸው አስተያየት፣ ሙሶሊኒ የሚጠብቀው አልነበረም።

ከዚህ ለዱቼ ከተሰጠው የታላቅ ክብርና የአድናቆት መግለጫ በኋላ፣ አዶልፍ ሂትለር ዓለምን ለመግዛት ወደፊት ስላለው ዕቅድ ምሥጢሩን በመጠኑ አወጣ። " ... **እኛ የምናስበውን ሁሉ በተግባር ለማዋል፣ ከእንግዲህ ወዲህ የሦስት ዓመታት ዝግጅት ይጠይቀናል። .... ይህም የዝግጅት ጊዜ ለእኛ ብቻ ሳይሆን፣ ለወዳጆቻችንም ጭምር የሚታሰብ ነው** ..... " በማለት፣ ከሙሶሊኒ ጋር ስለሚገነባው ጓደኝነት የመጀመሪያውን የምሥጢር ፍንጭ አወጣ። ጋሌአሶ ቺያኖ ይህንን ሁሉ በማስታወሻው ይዞ ወደ ሮማ ከተመለሰ በኋላ፣ ለፋሽስቱ መሪ ሪፖርት ሲያቀርብ፣ ሙሶሊኒን እጅግ አድርጐ የሚያረካው ሆነ። ፊዩረር ላለው ዕቅድ ሁሉ አብሬው እንድዋጋለት ሲጠይቀኝ፣ ለዝግጅት በቂ ጊዜ አይሰጠኝ ይሆናል በማለት፣ ዱቼ ሥጋት አድሮበት ነበር። አሁን ግን ሂትለር፣ እንኳንስ አብረውት ለሚሰለፉት ጓደኞቹ ቀርቶ፣ ለራሱም ቢሆን የሦስት ዓመታት የዝግጅት ጊዜ እንደሚያስፈልገው በመግለጹ፣ ለዱቼ ትልቅ ደስታ ሰጥቶታል። ይኸውም፣ በሚቀጥሉት ሦስት ዓመታት ውስጥ፣ ጣልያንም ትጥቋን ለማዘጋጀት በቂ ጊዜ ይኖራታል ብሎ በማሰብ ነው።

የሮማና የበርሊን አክስ (AXE) ከተመሠረተ ከጥቂት ቀናት በኋላ፣ በኅዳር 1936 ዓ.ም በሚላኖ አደባባይ ላይ ብዙ ሺህ ሕዝብ ሰብስቦ ሙሶሊኒ ባደረገው ንግግር፣ " .... **ወደፊት ሽቅብ ቀጥ ብሎ እንዲቆም የሚደረገው የበርሊንና የሮም የወዳጅነት ውል፣ እንደ ፎቶግራፍ በሩቅ እየታየ የሚኖር ብቻ አይደለም። በዚህ ውል ዙሪያ፣ የአውሮፓን አገሮች ሁሉ የሚሰበስብ ትልቅ ሰንሰለት የሚዘረጋበት ነው** .... " ብሎ ፎከረ። ይህ መግለጫ በፈረንሣይና በእንግሊዝ መንግሥታት ዘንድ ትልቅ ሐዘን የፈጠረ ነበር። ሙሶሊኒ፣ ምንም እንኳ አንድ ቀን ሊከዳቸው እንደሚችል ጥርጣሬ ቢኖራቸውም፣ እንዲህ በፍጥነት ወደ ሂትለር ይጠጋል ብለው

አልጠበቁም። እ.ኤ.አ መስከረም 28 ቀን 1937 ዓ.ም፤ ሙሶሊኒ የሂትለር እንግዳ ሆኖ ጀርመንን በአፊሲየል በጐበኘ ጊዜ፤ ሁለቱ ዲክታተሮች ባሳዩት መቀራረብና ባደረጓቸው ዲስኩሮች፤ የዴሞክራሲ አገሮች ሁሉ በጣልያን ላይ ምንም ዓይነት ተስፋ ማሳደር እንደሌለባቸው ለመገንዘብ የሚያስችላቸው ጊዜ ነበር ማለት ይቻላል። እነሱ ግን፤ ሙሉ በሙሉ ተስፋ ሳይቆርጡ በትዕግሥት መቆየትን መርጠዋል።

ፋሽስት ዱቼ የአፊሲየል ጉብኝቱን ለመጀመር በርሊን ሲደርስ፤ ናዚስቱ ፊዩረር አንድ ሚሊዮን ሕዝብ ሰብስቦ ባደረገለት ከፍተኛ አቀባበል ላይ፤ ጓደኛውን እንኳን ደህና መጣህ ሲለው፤ " .... **ይኸውና ! በዚህ ዓለም ካሉት ታላላቅ ሰዎች መካከል ብቸኛ የሆነ፤ ታሪክ ያልፈጠረው እሱ ራሱ ግን ታሪክን የሠራ ትልቅ መሪ አስተዋውቃችኋለሁ ....** " በማለት የተናገረው ቃል የሙሶሊኒን አእምሮ በደስታ ማዕበል ሲበጠብጠው ታዩ። ከዚሁ ደስታ ብዛት የተነሣም፤ ለሂትለር አስደናቂ ንግግር ሙሶሊኒ በዚያ ደካማ በሆነው ጀርመንኛ ቋንቋው የሰጠው መልስ፤ ወጉ የሚጠይቀውን ትቶ ስለራሱ ብቻ ተናገረ። " ... **አንድ ፋሽስት ወዳጅ ከያዘ፤ እስከ መጨረሻው ድረስ ወዳጅነቱን አጠንክሮ አብሮት ይጓዛል ....** " ካለ በኋላ፤ " .... **በዚህ ዓለም ካሉት አገሮች ሁሉ፤ ታላላቅና ዴሞክራት የሆኑት ጣልያኖችና ጀርመኖች ብቻ ናቸው። በዚህም አኳኋን መላዋ አውሮፓ ነገ ፋሽስት ትሆናለች ....** " በሚል ቃል ንግግሩን ዘጋ። ሙሶሊኒ ከመንቀዥቀዡና አእምሮው በደስታ ብዛት ከመናወጡ የተነሣ፤ ባደረገው ንግግር ውስጥ፤ ከዚህ በፊት ያልታየ ከፍተኛ አቀባበል ለማድረግ፤ በዕለቱ የነበረውን ዝናብና የብርድ ውሽንፍር ታግሶ፤ የተሰበሰበውን አንድ ሚሊዮን የጀርመን ሕዝብና መሪውን ፊዩረር ሂትለርን፤ ምንም ዓይነት ምስጋና ሳይሰጣቸው በመቅረቱ ያልተገረመ አልነበረም። አዶልፍ ሂትለር ግን፤ ከሙሶሊኒ የሚፈልገው ከዚህ የበለጠ ብዙ ነገር ስላለው፤ የዱቼን የተምታታ የቅሌት ዲስኩር በቁም ነገር አላዳመጠውም።

ሙሶሊኒ፤ የሂትለር የክብር እንግዳ ሆኖ በርሊን በቆየበት ጊዜ፤ ሁለቱ ዲክታተሮች ወደፊት የአውሮፓን ካርታ በምን አኳኋን ገነጣጥለው የናዚስቶችና የፋሽስቶች ተገዥ መሆን እንደሚችሉ በሰፊው ተወያይተዋል። ሆኖም፤ በዚያን ሰዓት ሂትለር፤ በጦር መሣሪያዎች ክምችትና በሠራዊት ኃይል ዝግጅት እጅግ በመገሥገስ ላይ ስለሆነ፤ ሙሶሊኒ በአድናቆት ከማዳመጥ በስተቀር፤ የጣሊያን አቅም የሚያኮራ ሆኖ እኔም በዚህ በኩል አለሁልህ የሚለው ነገር አልነበረውም። ሆኖም የዴሞክራሲ አገሮች የሚባሉትን ፈረንሣይንና እንግሊዝን በጣም የሚያሳስባቸውን፤ የሂትለርን ዋና ዋና ዕቅዶች ለምሣሌ፤ኦስትሪያን ከጀርመን ጋር ለማዋሀድ፤ ከቼኮዝሎቫኪያም መሠረታቸው ጀርመኖች ናቸው የሚባሉትን አውራጃዎች አስገድዶ ወደ ናዚው ግዛት ለማቀላቀል፤ ከዚያም አልፎ የፖላንድን ነፃነት ለማናጋት የመሰሰለውን በምሥጢር የተያዘ ሐሳብ ዱቼ ከሞላ ጐደል **በማወቁ**፤ ጉብኝቱን ፈጽሞ ወደ ሮማ ሲመለስ፤ በፓሪስና በሎንዶን መንግሥታት ላይ የማጭበርበሪያ ፖለቲካ ለመጫወት ሞክሮ ነበር።

እ.ኤ.አ የካቲት 12 ቀን 1938 ዓ.ም፤ አዶልፍ ሂትለር የኦስትሪያውን ቻንስለር በርሊን ድረስ እንዲመጣ አስጠርቶ፤ በቅርብ ጊዜ ውስጥ አገሩ ከጀርመን ጋር እንዲቀላቀል አስፈላጊ መሆኑን አስታወቀው። ይህ ዜና እንደተሰማ፤ ሙሶሊኒና የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ጋሌአሶ ቺያኖ፤ ሂትለር ሳያማክራቸው ቀጥታ የሆነ እርምጃ በመውሰዱ በመጠኑም ቢሆን ቅር ስለተሰኙ፤ የፊዩረርን ሐሳብ



አዶልፍ ሂትለር ሮም መጥቶ ሙሶሊንን ሲጎበኝ፣

ለጊዜው ለማደናቀፍ ከእንግሊዞች ጋር አንድ ዓይነት የሕብረት ግንኙነት ብንከፍት ይሻላል ብለው ተነሡ። ወዲያውም ከስድስት ቀናት በኋላ (የካቲት 18 ቀን) ሎንዶን ያለውን የጣልያን አምባሳደር ዲኖ ግራንዲን የታላቋ ብሪታንያ ጠቅላይ ሚኒስትር ቻምበርሌን፤ የውጭ ጉዳዩ አንቶኒ ኤደን ባለበት ተቀብሎ አነጋገረው።

" .... በሂትለር ምክንያት አሁን የምናየው የአውሮፓ ሁኔታ እጅግ አሥጊ እየሆነ መሄዱ አይሰማዎትም ወይ ? .... " ሲል፤ ቻምበርሌን ላቀረበለት ጥያቄ፤ የሙሶሊኒ አምባሳደር በሰጠው መልስ፤ ዋና ዋናዎቹ የአውሮፓ አገሮች ከተስማማንና ከተረዳዳን ለሚደርሰው ችግር መፍትሔ ማግኘት እንችገርም ነበር። ካለ በኋላ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ ያለውን የጣልያንን ይዞታ ቢያውቅለት፤ ዱቼ በማናቸውም መልክ ለመተባበር ዝግጁ መሆኑን ገለጸ። አንቶኒ ኤደን ይህን የመሰለውን ጉዳይ አጥብቆ የሚቃወም ስለሆነ፤ ጠቅላይ ሚኒስትር ቻምበርሌን በዚህ በቀረበው ሐሳብ ላይ ለመነጋገር ለጊዜው የማይቻል መሆኑን አስረድቶ የዱቼን አምባሳደር አሰናበተ። ከሁለት ቀናት በኋላ (የካቲት 20 ቀን 1938 ዓ.ም) የታላቋ ብሪታንያ ጠቅላይ ሚኒስትር ከሙሶሊኒ ጋር ተቀራርቦ ስምምነት ለማድረግ መፈለጉ ሲረጋገጥ፤ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አንቶኒ ኤደን " አልስማማም " ብሎ የሥራ መልቀቂያ ደብዳቤውን አቀረበለት። ጠቅላይ ሚኒስትሩም ከኮንሴርቫቲፍ ፓርቲ አባሎች መካከል ዋና ዋናዎቹ እነ ዊንስተን ቸርችል ስለሚደግፉት፤ ከኤደን መገላገሉን በደስታ ተቀብሉ፤ ሎርድ ሐሊፋክስን የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር አድርጐ ሾመው።

ቤኒቶ ሙሶሊኒ የኤደንን ከሥልጣን መልቀቅ ሲሰማ፤ ከመጠን በላይ ፈነደቀ። እስከዛሬ ድረስ የፋሽስት ጠላት በመሆን፤ ታላቋ ብሪታንያ ከጣልያን ጋር የወዳጅነትና የሕብረት ግንኙነት እንዳይኖራት በሩን ዘግቶ የያዘው አንቶኒ ኤደን ነበር። ከእንግዲህ ወዲህ ግን ምንም ዓይነት እንቅፋት አይገጥመንም በማለት፤ ከእንግሊዞች ጋር ስለሚያደርገው ስምምነት ዝግጅቱን አፋጠነ። ዱቼ እንደ ፈለገው፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት፤ ኢትዮጵያ የጣልያን መሆኗን በይፋ ካወቀ በኋላ፤ ሌሎቹም የሊግ ኦፍ ኔሽን አባል አገሮች ሁሉ የእንግሊዝን ምሳሌ ተከትለው ዕውቅና እንዲሰጡ ጥረት ለማድረግ ጠቅላይ ሚኒስትር ቻምበርሌን ተስማማ። ይህ ለሙሶሊኒ ትልቅ ድል ነበር። ከዚህ የበለጠ ምን ይፈልጋል ? ... በለውጡስ እንግሊዞች ከዱቼ ምን ለማግኘት ይጠብቁ ኖርዋል ? ...

ከጥቅምት 1936 ዓ.ም ጀምሮ፤ በሂትለርና በሙሶሊኒ መካከል የተመሠረተው የሕብረት ውል (AXE) ከጊዜ ወደ ጊዜ እየሰፋ መምጣቱ ግልጽ ቢሆንም፤ ዱቼ እስከምን ድረስ በፉሩሩ ዘንድ ተደማጭነት እንዳለው በትክክል ለማወቅ እንግሊዝና ፈረንሣይ መረጃ አልነበራቸውም። ሆኖም እጅግ ቢያንስ የፋሽስቱ መሪ የናዚስቱን ዲክታተር የቅርብና የሩቅ ፕላን የማወቅ ዕድል ስለአለው፤ ለዴሞክራሲ አገሮች የሚሰጣቸው መረጃዎች ከፍ ያለ ጠቃሚነት ይኖራቸዋል የሚል ተስፋ ነበራቸው። ከዚህም በላይ፤ ሂትለር ዕብደት በተጫነው መንፈሱ፤ አንድ ቀን ተነሳሥቶ በአውሮፓ ላይ የጦርነት እሳት ቢጭር፤ ሙሶሊኒ እኛን ትቶ አብሮት አይሰለፍም የሚለውን አስተያየታቸውን ቀጥለውበታል። ሂትለር ደግሞ በበኩሉ፤ በሙሶሊኒ ላይ ሙሉ በሙሉ እምነት ስላልነበረው፤ ስለአውሮፓ ጉዳይ የሚያስበውን ሁሉ ላይ ላዩን ካልሆነ በስተቀር፤ እውነተኛውን ጉዳይ ገልጦ እንደማይነግረው በብዙ ረገድ ታምኖበታል። ሆኖም፤ የበርሊንና የሮም ውል፤ የዴሞክራሲ አገሮችን ለማስፈራራት አመቺቷል።

# ምዕራፍ ፬

## ሂትለር እርምጃውን ቀጠለ
## የኦስትሪያ ነጻነት ተገፈፈ

እ.ኤ.አ በ1934 ዓ.ም አዶልፍ ሂትለር ሥልጣን በያዘ በዓመቱ፣ የትውልድ አገሩ የሆነችውን ኦስትሪያን ከጀርመን ጋር አቀላቅሎ ለመግዛት፣ የመጀመሪያ እርምጃው ለማድረግ ተነሥቶ ነበር። በዚያን ጊዜ የናዚስቱን ሐሳብ ለማክሸፍና የኦስትሪያን ነጻነት ለመጠበቅ፣ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ መንግሥታት ይበልጥ የፎከረውም ሆነ፣ በወሰኑ ላይ ወታደር ልኮ ናዚስቱን ዲክታተር ለማስፈራራት የሞከረው፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ነበር። ሂትለርም በዚያን ሰዓት ተቃዋሚዎቹ ብዙ ስለሆኑበት፣ አቅሙን ገምቶ ወደ ኋላ አፈገፈገ። አሁን ደግሞ በ1938 ዓ.ም፡-

1ኛ/ በቂ የጦር ኃይል ካደራጀ በኋላ፣

2ኛ/ የፋሽስቱን መሪ ከፈረንሣይና ከእንግሊዝ አለያይቶ ወዳጁ ካደረገው በኋላ፣ ከእንግዲህ ወዲህ ማን አለብኝ ? በማለት፣ ከጠዋቱ ሲያስብበት የኖረውን ጉዳይ ለመፈጸም ቆርጦ ተነሣ።

ኦስትሪያን ለመያዝ እርምጃ ከመውሰዱ ከሁለት ሳምንታት በፊት፣ ሂትለር ሙሶሊኒን ሲያታልለው ሁለት የተለያዩ መልዕክቶች ላከበት። እነዚህም፡-

የመጀመሪያው፣ " ... ከዛሬው ዕለት ጀምሮ፣ የጀርመን የጦር ኃይሎችን የበላይ አዛዥነት እኔ ራሴ መውሰዴን ለውድ ወዳጄ ለክቡር ዱቼ ስገልጽ፣ ደስታ ብቻ ሳይሆን ከፍተኛ ክብር ይሰማኛል ... " የሚል ሲሆን፣

ሁለተኛው ደግሞ፣ " ... የውድ ወዳጄ የክቡር ዱቼ ፈቃድ ቢሆንልኝ፣ በሚቀጥለው ግንቦት ወር ሁለተኛው ሳምንት ላይ፣ ውብ አገርዎን በኦፊሲየል ለመጐብኘት ያለኝን ጥልቅ ፍላጐት በታላቅ አክብሮት እገልጽልዎታለሁ .... " የሚል ነበር።

እነዚህን ሁለት ዓይነት መልዕክቶች፣ ቤኒቶ የተቀበለው በከፍተኛ ስሜትና ወሰን በሌለው ደስታ መሆኑን የሰጠው መልስ በግልጽ ያመለክታል።

1. " ... የጦር ኃይሎችዎን የበላይ አዛዥነት ሥልጣን መውሰድዎን የሰማሁት በታላቅ ስሜት ስለሆነ፣ ሁላችንንም እንኳን ደስ አለን እላለሁ። ቀጥሎም፣ ይህ እርስዎ የወሰዱት እርምጃ፣ በሁለታችን መካከል የተዘረጋውን የጓደኝነት ግንኙነት የሚያዳብረውና፣ በሁለቱ አገሮቻችን ባሉት የጦር ኃይሎቻችን መካከልም ያለውን ትብብር የሚያጠነክረው ይሆናል ብዬ ከልቤ አምናለሁ ... "

2. " ... ከዚህ ቀደም አገሬን በኦፊሲየል እንዲጐበኙ ያቀረብኩልዎትን የክብርና የወዳጅነት ጥሪ ተቀብለው፤ በመጭው ግንቦት ወር ሁለተኛው ሳምንት ላይ ጉብኝቱን ለመፈጸም ማሰብዎን ስሰማ፤ እጅግ የላቀ ደስታ ተሰምቶኛል። መላው የጣልያን ሕዝብ ከእኔ ጋር ሆኖ እርስዎን ለመቀበል የሚያደርገው ዝግጅት፤ ከዚህ ቀደም ለማንም ያላደረገው መሆኑን እንዲያውቁት እወዳለሁ ... "

ቤኒቶ ሙሶሊኒ፤ እነዚህን ሁለት መልዕክቶች ለሂትለር ካስተላለፈ በኋላ፤ የመጀመሪያ ሥራው አድርጐ የያዘው፤ ለናዚስቱ ዲክታተር አቀባበል የሚያስፈልገውን ዝግጅት ማከናወን ነበር። ሌሎች ሥራዎች ሁሉ ለጊዜው እንዲቆሙ ተደርገው፤ የሮማ ከተማ እንዴት አድርጋ በነጭ ቀለም እንደምታሸበርቅና፤ ለታላቁ ናዚ ምን የተለየ ነገር ለማሳየት እንደምትችል፤ የኪነ ጥበብ ዐዋቂዎች ሌት ተቀን እየተሰበሰቡ እንዲያጡኑና ፕላኑን እንዲያቀርቡ ታዘዙ። ዱቼም ዐዋቂዎቹ የሚነድፉለትን ፕላን ሁሉ አንድ በአንድ እየመረመረ የሚወስነው እሱ ብቻ ስለነበረ፤ ለሌሎቹ ሥራዎቹ ፋታ አላገኘም። ከዚህም የመስተንግዶ ዝግጅት የተነሣ፤ የኦስትሪያ ጉዳይ በፋሽስቱ መሪ በኩል ጨርሶ ተረስቶ ነበር።

አዶልፍ ሂትለር ኦስትሪያን አስገድዶ ነፃነቷን ለመግፈፍና ከጀርመን ጋር ለማቀላቀል፤ የናዚስቶቹን ሚሊሺያኖችና የጦር ወታደሮቹን ዝግጅት አጠናቅቆ፤ እርምጃ ከመውሰዱ ከሠላሳ ስድስት ሰዓቶች በፊት ለቤኒቶ ሙሶሊኒ የሚከተለውን መልዕክት ላከለት።

<u>ክቡር ዱቼ !</u>

" .... የትውልድ አገሬ በሆነችው በኦስትሪያ ላይ ሰላምና ፀጥታ እንዲመሠረት እርምጃ ወስጃለሁ። ይህንንም በመጀመሪያ እንዲያውቁት የማደርገው፤ ለርስዎ ለወዳጄ ለታላቁ ዱቼ፤ የጣልያን ፋሽስት መሪ ነው። ከዚህም ጋር እያይዤ የምገልጽልዎ፤ አንደኛ፤ ያደረግኩት ውሳኔ ተገቢና ትክክለኛ መሆኑን እንዲያውቁልኝ ሲሆን፤ ሁለተኛ ደግሞ፤ ከዚህ ቀደም ከርስዎ ጐን ቆሜ በማናቸውም ችግርዎ ወዳጅነቴን እንዳሳየሁት ሁሉ፤ ወደፊትም ያለ አንዳች እንከን ወዳጅነቴን የምቀጥል መሆኑን እንዲረዱልኝ ነው .... "

ይህ መልዕክት ለሙሶሊኒ የቀረበው፤ የጣልያኑ ንጉሥ የቪክቶር አማኑኤል ሣልሳዊ አማች በሆነው በጀርመናዊው ናዚስት በልዑል ፊሊፕ ደ-ሄስ (Prince Philippe De Hess) አማካይነት ነበር። ሙሶሊኒም ወዲያውኑ በሰጠው አጭር መልስ፤ " ... የኦስትሪያ ጉዳይ በእኔ በኩል ለጊዜው ችግር አይፈጥርብኝም ... " የሚል በመሆኑ፤ በፉዩረር ላይ ትልቅ ደስታ ፈጠረ። ሂትለርም በበኩሉ፤ " ... ታላቁ ወዳጄ ዱቼ፤ ይህንን የጣሉብኝን ከፍተኛ ውለታ መቸውንም አልረሳውም ... " በሚል ቃል የጋለ ምስጋናውን አቀረበ። ይህ ከሆነ በኋላ፤ ናዚስቶቹ የኦስትሪያን ዋና ከተማ ቪየናን አተራምሰው ከመያዛቸው በፊት፤ በቦታው ላይ የነበረው የመንግሥቱ መሪ " ሹሽኒግ " (Schuschnigg) ወደ ሮም እየደወለ፤ እንደ ድሮው መስሎት ሙሶሊኒን ለማነጋገር ቢሞክር የሚመልስለት አጣ።

በዚህ አሳዛኝ ሁኔታ መካከል የሙሶሊኒ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ጋሌአሶ ቺያኖ፣ አንድ ሐሳብ በድንገት ፈለቀለት። ሂትለር ኦስትሪያን ወደ ጀርመን ሲያቀላቅል፣ ዱቼ በዝምታ በማለፍ ከፍ ያለ እርዳታ ስለሰጠው፣ ፋሽስታዊት ጣልያን ደግሞ ኢትዮጵያን እንደ አደረገችት፣ የአልባኒያን ንጉሣዊ አገር ወደ ግዛቷ ለማስገባት እንድትችል፣ ፊዩረር ድጋፉን መስጠት አለበት አለ። ይህንን የቺያኖን አስተያየት ሂትለር ሮም ባለው አምባሳደሩ በኩል እንደሰማ የሰጠው መልስ፣ " ችግር የለም " የሚል ነበር። የቺያኖ ሐሳብ ወዲያውኑ ባይፈጸምም፣ ከአንድ ዓመት በኋላ፣ በ1939 ዓ.ም አልባኒያ በፋሽስት ጦር ተወግታ የጣልያን ኢምፓይር አባል ተብላለች።

መጋቢት 14 ቀን 1938 ዓ.ም ማታውኑ፣ ሂትለር በከፍተኛ የጦር አጀብ ከኦስትሪያ ግዛት ገብቶ በተወለደበት ከተማ ካደረ በኋላ፣ በማግሥቱ መጋቢት 15 ቀን በቪየና ከተማ በሚሊዮን የሚቆጠር ሕዝብ በተሰበሰበበት፣ ከዚህ ዕለት ጀምሮ የኦስትሪያኖችንና የአገራቸውን ጀርመንነት በይፋ አወጀ። ከአራት ዓመታት በፊት፣ በተለይም ከ1934 ዓ.ም እስከ 1936 ዓ.ም ድረስ፣ የኦስትሪያን ነፃነት ላለማስነካት፣ ሙሶሊኒ ያደረጋቸው ዲስኩሮችና ይወስዳቸው የነበሩት እርምጃዎች ዛሬ የት ደረሱ ? እየተባለ በዓለም ላይ በሰፊው ሲተረክ፣ ከራሱ ከዱቼ ሆነ ወይም ከአማቹ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ቺያኖ አንዳች መልስ አልተሰጠም። " ... የኦስትሪያ ነፃነት እስከዛሬ በጣልያን ተጠብቆ የቆየና፣ ወደፊትም ሳይደፈር ተጠብቆ የሚኖር ነው .... " በማለት በ1934 ዓ.ም ዱቼ እያከታተለ ይሰጥ የነበረውን መግለጫ፣ ኦስትሪያኖች ብቻ ሳይሆኑ፣ የሌላው ዓለም ሕዝብና በተለይም ጀርመኖች በትክክል የሚያስታውሱት ነበር። ዛሬ ግን ይህ ሁሉ በፊዩረር ወዳጅነት ስለተለወጠ፣ ኦስትሪያን እኔ አላውቅሽም ብሏታል። በ1936 ዓ.ም፣ የኢትዮጵያን ነፃነት ለመደምሰስ ሲኖር ዱቼ ሕዝባችንን በጋዝ መርዝ በሚያነድበት ጊዜ፣ በሊግ ኦፍ ኔሽን ሸንጐ ላይ የፋሽስት ደጋፊ ሆኖ ይጨፍርብን የነበረው የኦስትሪያ መንግሥት፣ አንድ የመከላከያ ጥይት ሳይተኩስ የነፃነት ልብሱን አውልቆ ለሂትለር አስረከበ። የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታትም፣ ሂትለር ነገ ለእነሱም እንደማይተኛላቸው ቢያሳስባቸውም፣ በኦስትሪያ ነፃነት መገፈፍ ጉዳይ፣ ተቃውሞአቸውን አጠንክረው ከመግለጽ በስተቀር፣ ከዲክታተሩ ጋር ጦርነት ማንሣት አልፈለጉም። በዚህ አጋጣሚ ሂትለር፣ የመጀመሪያውን ምኞቱን እንደ ፈለገው ፈጸመ።

# ምዕራፍ ፳

## ከኦስትሪያ ወደ ቼኮስሎቫኪያ
## አስደናቂው የ "ሙኒክ" ጉባኤ

ጀርመንና ኦስትሪያ የዘር፣ የባህልና የቋንቋ አንድነት ስለአላቸው፣ በአንድ መንግሥት ውስጥ ተጠቃልለው መተዳደር አለባቸው በሚል ዕምነት፣ መጋቢት 15 ቀን 1938 ዓ.ም፣ አዶልፍ ሂትለር የነፃይቱን ኦስትሪያ መብት በመድፈር እርምጃ ሲወስድ፣ ምንም ዓይነት ተቃውሞ እንዳልገጠመው ከዚህ በፊት በነበረው ምዕራፍ ተመልክተናል። በዚህ አኳኋን፣ በኦስትሪያ ጉዳይ ላይ ያገኘው ውጤት በጣም ስለአበረታታው፣ ፊዩረር ሂትለር የ3ኛውን የጀርመን ኢምፓይር ለማስፋፋት የጀመረውን ጉዞ አፋጠነ።

የኦስትሪያን ነፃ መንግሥትነት ከደመሰሰ ከስድስት ወራት በኋላ፣ ናዚስቱ ዲክታተር ፊቱን ወደ ቼኮስሎቫኪያ አዙሮ፣ በዚች አገር ውስጥ የጀርመን ተወላጆች ይኖሩበታል የሚባሉትን የሱዴትን (Sudetes) አውራጃዎች ለመቀማትና ወደ ግዛቱ ለማጠቃለል እፈልጋለሁ አለ። እነዚህም በሱዴት አውራጃ ውስጥ የሚገኙት፣ ቦሄም፣ ሞራቪ፣ ግሮስደችላንድ (BOHÊME-MORAVIE-GROSSDEUTSCLAND) የሚባሉት ናቸው። ቼኮስሎቫኪያ፣ ቀደም ሲል ከሶቪየት ሕብረትና ከፈረንሣይ መንግሥት ጋር የቃል ኪዳን ትብብር ስምምነት ቢኖራትም፣ ለአሁኑ ችግሯ በእነዚህ ወዳጅ በተባሉ አገሮች መተማመን አልቻለችም። የፈረንሣይ መንግሥት፣ ሂትለር ከመጀመሪያው የዓለም ጦርነት በኋላ፣ በአገሩ በጀርመን ላይ ያደረሰውን በደል ብድር ለመመለስ እንደሚያስብ ቢያውቅም፣ በዚህ ሰዓት ሰላማዊነትን ከማሳየት በስተቀር ለቼኮስሎቫኪያ ሲል ከፊዩረር ጋር ጠብን አይፈልግም። የታላቋ ብሪታንያም መንግሥት ከዚህ የተለየ አቋም የለውም። ስለዚህ፣ የፕራግ መንግሥት ያለው ምርጫ፣ ባለው አቅም እስከሚቻለው ድረስ ነፃነቱንና መብቱን ለማስከበር መታገል ስለሆነ፣ የሂትለርን ዛቻ አልቀበልም የሚል መግለጫ አወጣ። ወዲያውም፣ መስከረም 21 ቀን 1938 ዓ.ም፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ በአንድነት ሆነው፣ ለቼኮስሎቫኪያ መንግሥት ባስተላለፉት መልዕክት፣ ከሂትለር ጋር ወደ ጠብ ማምራቱ ጠቃሚ ስላልሆነ፣ ለችግሩ ሰላማዊ መፍትሔ እንዲገኝለት መተባበሩ ይሻላል ሲሉ አስጠነቀቁ። ሲላውም ወዳጅ የተባለው የመስኮብ መንግሥት ግንኙነቱን እያቀዘቀዘ ወደ ኋላ ስለአፈገፈገ፣ ቼኮስሎቫኪያ ብቻዋን ቀረች።

መስከረም 28 ቀን 1938 ዓ.ም፣ የአዶልፍ ሂትለር የቅርብ ጓደኛ የሆነው ቤኒቶ ሙሶሊኒ፣ ፊዩረር ዛሬ የጠየቀውን ባይሰጡት፣ ነገ ብድግ ብሎ ቼኮስሎቫኪያን በሙሉ ከመያዝ ስለማይመለስ፣ የአራቱ ታላላቅ አገሮች የፈረንሣይና የእንግሊዝ፣ የጣልያንና የጀርመን መሪዎች በአስቸኳይ ተሰብስበው አንድ መፍትሔ እንዲሰጡ በጥብቅ አሳሰበ። ከፋሽስቱ መሪ የቀረበውን ሐሳብ እንግሊዝና ፈረንሣይ ወዲያውኑ ሲቀበሉ፣ ሂትለርም ስብሰባው በራሱ አገር "ሙኒክ" ላይ የሚደረግ ከሆነ እስማማለሁ አለ። የናዚስቱን ጥሪ ሁሉም ተቀብለው ጉዞአቸውን ወደ ሙኒክ ሲቀጥሉ፣ ሂትለርን በመፍራት ብቻ ዋናዋ ባለጉዳይ የሆነችው ቼኮስሎቫኪያ

በስብሰባው ላይ ተካፋይ እንድትሆን፣ ፈረንሣይና እንግሊዝ እርምጃ ሳይወስዱ ቀሩ። በመሠረቱ፣ የስብሰባው ዋና ዓላማ፣ በጀርመንና በቼኮዝሎቫኪያ መንግሥታት መካከል ለተፈጠረው ችግር መፍትሔ ለመፈለግ ከሆነ ሁለቱም ባለጉዳዮች በእኩል ደረጃ መካፈል ነበረባቸው። ነገር ግን፣ ዳኝነቱ የሚዘጋጀው ግፈኛው የሚቀበለውን መንገድ በመምረጥ ብቻ ስለሆነ፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ ለተጠቂዋ አገር መብት ፊት ለፊት ለመሟገት አልፈለጉም። በዚህ ዓለም ብዙ ጊዜ ፍትሕ የሌለው የፖለቲካ ታሪክ እየተደጋገመ ሲፈጸም ታይቷል። ለምሳሌም፣ በ1935 ዓ.ም ሙሶሊኒ ኢትዮጵያን ቅኝ ግዛቱ ለማድረግ በጦርነት በሚያጠቃበት ጊዜ፣ እንግሊዝና ፈረንሣይ መፍትሔ እንፈልጋለን በማለት ከፋሽስቱ መንግሥት ጋር ስብሰባ እያዘጋጁ በሚነጋገሩበት ጊዜ፣ ኢትዮጵያን ለወጉ እንኳ ሐሳቧን ቀርባ እንድትገልጽ አይጠሯትም ነበር። አሁንም ቼኮስሎቫኪያን እንደ ኢትዮጵያ ለግፈኛው መንግሥት በመገበር፣ ሰላም እንመሠርታለን የሚል ሕልም ስለአደረባቸው፣ ከአራት ዓመታት በፊት የፈጸሙትን በደል እንደገና መድገማቸውን አስመስክረዋል።

ሙሶሊኒ ባቀረበው ሐሳብ መሠረት፣ መስከረም 29 ቀን 1938 ዓ.ም፣ የአራቱ የአውሮፓ መንግሥታት መሪዎች፣ ጀርመኑ ፊዩረር፣ ፋሽስቱ ዱቼ፣ እንግሊዙ ኔቪል ቻምበርሌን፣ ፈረንሣዩ ኤድዋርድ ዳላዲዬ፣ በሂትለር አገር በሙኒክ ከተማ ተሰበሰቡ። ከስብሰባው በፊት፣ የሂትለር ዋና ዓላማ ቼኮስሎቫኪያ የምትባለዋን አገር፣ ነፃነቷን ደምስሶ የጀርመን ግዛት ለማድረግ መሆኑን ያልተገነዘበ አልነበረም። ነገር ግን፣ አዶልፍ ይህን የተለመውን ለመፈጸም ቀጥታ የኃይል እርምጃ ከመውሰዱ በፊት፣ የዴሞክራሲ አገሮችን ለማታለል፣ በቼኮስሎቫኪያ ውስጥ ያሉት የጀርመን ተወላጆችና የሚኖሩባቸው የሱዴት አውራጃዎች ወደ እናት አገራቸው ከተቀላቀሉ፣ ሌላ በተጨማሪ የምጠይቀው ነገር የለም አለ። የእንግሊዝና ፈረንሣይም ዓላማ ለጊዜው ሰላምን በተቻለ ያህል ማቆየት ስለሆነ፣ ምንም ሳያንገራግሩ ከቼኮስሎቫኪያ ግዛት ላይ ለመውሰድ የጠየቅከውን እንደግፋለን አሉት። ፊዩረር ይህን አስተያየት ያዳመጠው፣ እጅግ በተገረመ ስሜት ነበር። ለካስ ! እንዲህ በቀላሉ ሐሳቤን አሜን ብለው የሚቀበሉ መሆናቸውን ባውቅ ኖሮ፣ የበለጠ መጠየቅ ነበረብኝ የሚል ቁጭት አሳደረበት። በዚሁ ጊዜ፣ ሙሶሊኒ ማህል ቤት ገብቶ ሲያምታታ፣ " ... ክቡር ፊዩረር እኮ ዋናው ዓላማቸው፣ የአገራቸውን መብትና ዕድገት መጠበቅ ቢሆንም፣ የአውሮፓ አገሮች ሰላምና ደህንነት እንዲጠበቅ፣ ምንጊዜም ከእኛ ጋር ለመተባበር ዝግጁ ናቸው ... " የሚል የማይታመን አጉል ፕሮፓጋንዳ ተናገረ። ሂትለርም መልስ ሲሰጥ፣ " ... አሁን ወዳጄ ወንድሜ ዱቼ እንደተናገሩት፣ እያንዳንዳችን ቅድሚያ የምንሰጠው ምንም እንኳ ለየአገራችን ደህንነትና ዕድገት ቢሆንም፣ አንዳችን የአንዳችንን ችግር እየተወያየን ለጋራ ጥቅማችን ብንተባበር፣ መላዋ አውሮፓ ብቻ ሳትሆን መላዋ ዓለም ተጠቃሚ መሆን ትችል ነበር ... " የሚል ከልብ ያልመነጨ የስብከት ቃል ወረወረ። የዋሁ የእንግሊዝ ጠቅላይ ሚኒስትር ኔቪል ቻምበርሌንም፣ "ሂትለር ከፍ ያለ የተከበረ ሰው ነው" የሚል ለጆሮ የሚከብድ፣ ተቀባይነት የሌለው ቅጽል አሸከመው።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ መጀመሪያ አዶልፍ እንደጠየቀው፣ በቼኮስሎቫኪያ ውስጥ የሚገኙት የጀርመን ተወላጆች የሚኖሩባቸው ናቸው የሚባሉት የሱዴት አውራጃዎች ሁሉ፣ ለሂትለር እንዲሰጡ፣ በስብሰባው ላይ ተካፋዮች የሆኑት አገሮች ሁሉ ስለተስማሙ፣ የ "ሙኒክ ጉባኤ" ለዓለም ሰላም መድኃኒት ሆኗል የሚል ሥያሜ ተሰጠው። እዚህ ላይ በጣም የሚያሳዝነው፣ የዓለምን ሰላም ቋሚ ለማስደረግ ሙኒክ ላይ ተገኘ የተባለው መድኃኒት፣ ምን ኖርዋል? ተብሎ ቢጠየቅ፣

ጉልበተኛው የፈለገውን አሜን ብሎ ከመቀበል በስተቀር፤ ሌላ የተፈጸመ ምንም አዲስ ነገር እንደሌለ ለማንም ግልጽ ነው። እዚህ ላይ ከታላቋ ብሪታንያ ከታወቁት የፖለቲካ መሪዎች መካከል አንድ ሰው ብቻ፤ ዊንስተን ቸርችል፤ ለሙኒክ ጀግኖች የገለጸው አስተያየት፤ በዓለም ታሪክ ውስጥ የተመዘገበ ስለሆነ፤ ሊጠቀስ የሚገባው ነው። " ... ውርደትን የመረጣችሁት፤ ሕዝባችንን ከጦርነት ለማዳን ነው ብላችኋል። ነገር ግን፤ ውርደቱን ተቀብላችሁ ጦርነቱም እንደማይቀርላችሁ ዕወቁት ... " ይህ የቸርችል ቃል፤ ከግቡ ደርሶ ለመታየት ከአንድ ዓመት የበለጠ ጊዜ አልወሰደም። የሙኒክ ጉባኤ በመስከረም 29 ቀን 1938 ዓ.ም ተከናወነ። የዓለም ጦርነት ደግሞ ልክ በዓመቱ በመስከረም 3 ቀን 1939 ዓ.ም ተጀመረ። በመስከረም 30 ቀን 1938 ዓ.ም ሙኒክ ላይ የዓለም ሰላም እንደገና ተመሠረተ ተብሎ፤ ያ ሁሉ ዲስኩር ከተነዛ ከስድስት ወራት በኋላ፤ ፊዩረር የሰጠውን ቃልና የፈረመበትን ሰነድ በመካድ፤ የቼኮስሎቫኪያን ነፃነት ደምስሶ የራሱ ግዛት ለማድረግ ተነሣ። በዚህ ጊዜ የዴሞክራሲ አገሮች በኦስትሪያ ላይ እንዳደረጉት ሁሉ፤ ወይ ጉድ ? ብለው ዝም ከማለት፤ የተቃውሞ እንቅስቃሴ ቢያደርጉ ኖሮ፤ አዶልፍ ይህን ያህል የልብ ልብ አይሰማውም ነበር። እሱ ግን ደካማነታቸውን በሚገባ ስለተረዳው፤ የጀመረውን ወደፊት እየገፋ ከመቀጠል አላመነታም።። መጀመሪያ የስሎቫኪያን አውራጃ ከቼክ ግዛት በማስገንጠልና የናዚስቶች ተከታዮች የሆነ መንግሥት በማቋቋም፤ ቀጥሎ ደግሞ በቼክ ግዛት ውስጥ የሂትለር ደጋፊ የሆነ አስተዳደር በመመሥረት፤ አገሪቱን ከከፋፈለ በኋላ፤ መጋቢት 15 ቀን 1939 ዓ.ም የሂትለር ጦር ፕራግ በመግባት ቼኮስሎቫኪያ ተብሎ የሚጠራውን ነፃ መንግሥት ደምስሶ ያዘ።

ከስድስት ወራት በፊት፤ የእንግሊዝና የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትሮች ከፋሽስቱ ጣልያን ጋር ሆነው፤ በሙኒክ የቼኮስሎቫኪያን ነጻነት ለናዚስቱ ዲክታተር አስረክበው ወደ አገራቸው ሲመለሱ፤ "ሰላምን ያዳኑ" እየተባሉ ከየሕዝባቸው የተሰጣቸውን አድናቆት በዚያን ጊዜ ሲያስታውሱት፤ ምን ተሰምቷቸው ይሆን ? .... ያለ ጥርጥር የሠሩት ሁሉ በታሪክ ላይ አሣፋሪ ሆኖ እንደ ተመዘገበባቸው ሳያስቡት አልቀሩም። ታሪኩን ወደ ኋላ መለስ ብለን ብንመለከት፤ ከመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ በኋላ፤ በ1919 ዓ.ም በቬርሣይ የሰላም ውል ሲደረግ፤ የኦስትሪያ ሀንጋሪያ ዳይናስቲ ተገዥዎች የነበሩት፤ የቼክና የስሎቫክ ሕዝቦች በአንድነት ተዋህደው "ቼኮስሎቫኪያ" በሚል መጠሪያ ነፃ መንግሥት አድርገው ያቋቋሟቸው ዋናዎቹ ፈረንሣይና እንግሊዝ ነበሩ። አሁን ደግሞ ልክ ከሐያ ዓመታት በኋላ፤ (1919 - 1939) ናዚስቱ ሂትለር እነዚህን የቼክና የስሎቫክ ሕዝቦች ከአንድነታቸው ለያይቶ፤ የነበራቸውንም ነፃነት ገፍፎ፤ የጀርመን ተገዢዎች ሲያደርጋቸው፤ ያልተሟገቱና ዝም ብለው የተመለከቱ እነዚሁ ፈረንሣዮችና እንግሊዞች ሆነው ተገኙ።

እንግዲህ! የደረሰ ደርሷል። የወደፊቱና በቅርቡም የሚቀጥለው የሂትለር ዕቅድ ምን ይሆን? ተብሎ ቢጠየቅ፤ እርምጃው እየገፋ መሄዱን እንጂ፤ መቆሚያው የት ላይ እንደሚሆን አውቃለሁ የሚል በዚያን ጊዜ አልተገኘም ነበር። እንደሚታየው ቼኮስሎቫኪያ፤ ከሦስት ዓመታት በፊት ለኢትዮጵያ የደረሰውን ጽዋ እሷም እንዳይቀርባት አግኝታለች። ዊንስተን ቸርችል እንዳለውም፤ የዲክታተሩን ፍላጐት ስናሟላ ሰላም ይወርድልናል ብለው ውርደትን የመረጡት የዴሞክራሲ አገሮች፤ ከወርደቱም ጋር ከጦርነቱ እንዳላመለጡ የደረሰው ታሪክ ደህና አድርጉ አሳይቷል።



"ሙኒክ" ላይ በሙሶሊኒ ሊቀመንበርነት በተደረገው ስብሰባ፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት፤ ቼኮስሎቫኪያን ለሂትለር አስረክበው ዓለም ሠላም ሆነች ብለው ተደሰቱ፤



ከሙኒክ ስብሰባ በኋላ ሂትለር ለሙሶሊኒ ያደረገው ያሸኛኘት ሥነ ሥርዓት፤

# ምዕራፍ ፲

## ፖላንድ ፤ የሁለተኛው የዓለም ጦርነት መክፈቻ ሆነች

አዶልፍ ሂትለር በአንድ ዓመት ጊዜ ውስጥ የኦስትሪያንና የቼኮዝሎቫኪያን መንግሥታት ነፃነት ደምስሶ ተገዥዎቹ ካደረጋቸው በኋላ፤ የሚቀጥለው እርምጃው ፖላንድን መውረር ሆነ። የዓለም መሪ ለመሆን ከፍተኛ ምኞት ያደረበት ዲክታተር፤ በቼኮዝሎቫኪያ ላይ እንዳደረገው ሁሉ፤ ፖላንድን ለመያዝ የፈጠረው ሰበብ፤ በዚህች አገር ውስጥ የጀርመን ተወላጆች የሚኖሩባቸው አንዳንድ አውራጃዎችና በተለይም ዳንትዚግ (Danzig) የተባለው ወደ ባሕር መተላለፊያ ኮሪዶር፤ በቬርሣይ ውል አለአግባብ ከጀርመን ተነጥቀው ለፖላንድ የተሰጡ ስለሆኑ፤ እንዲመለሱልኝ ያስፈልጋል በማለት ነበር።

እንደሚታወቀው፤ ይህች ያልታደለች "ፖላንድ" የተባለች አገር፤ እስከ መጀመሪያው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ ድረስ፤ ለአንድ መቶ ዓመታት ጥንታዊው ነፃነቷ ተገፍፎ፤ በጀርመን፤ በኦስትሪያ፤ በሀንጋሪያና በመስኮብ የሮማኖቭ ዲይናስቲዎች፤ ለሦስት ተከፍላ ስትገዛ የኖረች ነበረች። የመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ድል አድራጊዎች በ1919 ዓ.ም ቬርሣይ በሚገኘው የፈረንሣይ ቤተመንግሥት ተሰብስበው ባቀናጁት የሰላም ውል፤ ፖላንድ ከጀርመን፤ ከኦስትሪያና ከመስኮብ ተገዥነት ተላቅቃ ከመቶ ዓመታት በፊት የነበራት ነፃነት እንዲመለስላትና መንግሥቷን እንድታቋቁም አደረጉላት። ቀደም ሲል እንደተገለጸው፤ በቬርሣይ ጉባኤ የተወሰኑትን ሁሉ በየተራ ለማፍረስ ታጥቆ የተነሣው አዶልፍ ሂትለር፤ መስከረም 1 ቀን 1939 ዓ.ም ባልተጠበቀ ሌሊት ፖላንድን መውረር ሲጀምር፤ የፈረንሣይና የእንግሊዝ መንግሥታት የሚቀጥለው የናዚስቱ ዕቅድ ወደ እኛ የሚያተኩር ነው ብለው ደነገጡ። ሂትለር በፖላንድ ላይ በወሰደው እርምጃ፤ ከእንግዲህ ወዲህ ምንም ዓይነት ሰላም ሊኖር እንደማይችል ስለታያቸው፤ የዴሞክራሲ አገሮች ከናዚስቱ መንግሥት ጋር ለመዋጋት መቁረጣቸውን መስከረም 3 ቀን 1939 ዓ.ም፤

- ታላቋ ብሪታንያ ከእኩለ ቀን በፊት በ5 ሰዓት፤
- ፈረንሣይ ከእኩለ ቀን በኋላ በ11 ሰዓት

መግለጫ ሲሰጡ፤ የሁለተኛው የዓለም ጦርነት መጀመሩ ይፋ ሆነ።

በዚች በአሳዛኟ በፖላንድ ጉዳይ፤ እንግሊዝና ፈረንሣይ ከናዚስቱ ዲክታተር ጋር ጦርነት ማድረጋቸው እንደማይቀር በሚመካከሩበት ጊዜ፤ የሶቪየት ሕብረት መንግሥት አብሮን ይሰለፋል የሚል ዕምነት ነበራቸው። ነገር ግን፤ ፖላንድ ከመወረሯ ዐሥር ቀናት በፊት፤ የጀርመንና የመስኮብ መንግሥታት በመካከላቸው ከሰላም በስተቀር ጠብና ጦርነት እንዳይኖር ውል ሲፈራረሙ፤ ስታሊን ከዴሞክራሲ አገሮች ጋር እንደማይሰለፍ ተረጋገጠ። በዚህ ጊዜ በሎንዶንና በፓሪስ የተፈጠረው

ቅሬታ ቀላል አልነበረም። ነሐሴ 23 ቀን 1939 ዓ.ም፤ ሂትለርና ስታሊን ይህንን የሰላም ውል ሲያደርጉ በናዚስትና በኮሙኒስት መሪዎች መካከል ለምን ጊዜውም፤ ከልብ የመነጨ ፍቅርና መግባባት ይኖራል ተብሎ እንደማይታሰብ፤ የታወቀ ነበር። ለጊዜው ግን፤ የዴሞክራሲ አገሮችን ያሳዘናቸው፤ በስታሊን መከዳት ብቻ ሳይሆን፤ በተፈራረሙት ውል ላይ የፖላንድን ግዛት ሁለቱም አገሮች በየጥቅማቸው አኳያ ለመከፋፈል ተስማምተው መገኘታቸው ነው። በዚህ ስምምነት መሠረት፤ ሂትለር በሚፈልገው ዓይነት ከፖላንድ ግዛቶች ውስጥ ይጠቀሙኛል የሚላቸውን አውራጃዎች ወደ ጀርመን ሲያቀላቅል፤ ስታሊንም በበኩሉ አንዳንዶቹን ግዛቶች ወደ ሶቪየት ሕብረት ክልል ውስጥ ለማስገባት ቻለ። ከዚህም በቀር ስታሊን ከሂትለር ጋር ባደረገው የወዳጅነት ውል በመጠቀም፤ ከብዙ ጊዜ ጀምሮ ሲመኛቸው የነበሩትን፤ ኢስቶኒ፣ ሌቶኒ እና ሊቱዋኒ (L'Estonie, La Lettonie et Lituanie) የተባሉትን ነፃ መንግሥታት፤ በጦር ኃይል በየአገራቸው ውስጥ የኮሙኒስት ሬቮሉሽን አስነሥቶ የታላቁ የሶቪየት ሕብረት ሬፑብሊክ አባል እንዲሆኑ የብረት መጋረጃውን ዘረጋባቸው።

አዶልፍ ሂትለር ከመስከረም እስከ ጥቅምት 1939 ዓ.ም ድረስ ባለው በአንድ ወር ውስጥ የፖላንድ ወረራውን ካጠናቀቀ በኋላ፤ ጦሩን ወደ ሰሜን አውሮፓ በማሻገር ዴንማርክንና ኖርዌይን፣ ከዚያም ለማንም ወገን በጦር የማይሰለፉ ኒውትራል መሆናቸውን አስታውቀው፤ በሰላም የተቀመጡትን ቤልጂክን፣ ሉክሳምቡርግንና ሆላንድን በግንቦት 1940 ዓ.ም ወግቶ ያዘ። ይህ ሁሉ ያለ አንዳች ችግር ከተሳካለት በኋላ፤ የአዶልፍ ሂትለር ትልቁ የጦር ኃይል ወደ ፈረንሣይ አመራ። በዚህ ጊዜ፤ ያ የተፈራው ደረሰ። ....

## ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር ተሰለፈ

ናዚስቱ ዲክታተር፤ ፖላንድን ከመውረሩ ከጥቂት ቀናት በፊት ነሐሴ 25 ቀን 1939 ዓ.ም ለወዳጁ ለፋሽስቱ መሪ ውሳኔውንና ዝግጅቱን የሚገልጽ ቴሌግራም በላከለት ጊዜ፤ ጣልያን አሁኑኑ ከጀርመን ጋር ጦርነቱ ውስጥ መግባት አለባት ይለኛል ብሎ፤ ሙሶሊኒ ከፍ ያለ ሥጋት ስለአደረበት፤ የሚከተለውን አስቸኳይ መልዕክት ለሂትለር አሳለፈ።

.... ጣልያን ከወዳጇ ከሂትለር ጋር በጦር ሜዳ ለመሰለፍ ዝግጅቷን የምታጠናቅቀው፤ ከሦስት ዓመታት በኋላ በ1942 ዓ.ም እንደሚሆን አረጋግጬልዎ ነበር። አሁን ግን በርስዎ በኩል እርምጃው ሲፋጠን፤ በእኔ በኩል ደግሞ ዝግጅቱ ስላልተሟላልኝና ብዙ መሣሪያዎች ስለጐደሉኝ፤ ከልብ ከመነጨውና ፍጹም ታማኝ ከሆነው ወዳጅነቴ ጋር ችግሬን እንዲረዱልኝ እለምናለሁ .... ሲል፤ ዱቼ አመለከተ። ሂትለርም ይህ መልዕክት እንደ ደረሰው፤ ወዲያውኑ በሰጠው መልስ፤ " ... ለዝግጅቱ የሚያስፈልግዎትን ሁሉ ዘርዝረው ቢገልጹልኝ፤ የሚቻለውን ሁሉ በቶሎ እንዲያገኙ ለማድረግ ጥረት አደርጋለሁ ... " አለው።

ዱቼ ጉድ ፈላበት። ነብሩ ሂትለር አልለቀቀውም። ስለዚህ፤ ታላላቅ ጄኔራሎቹንና የሚሊታሪ ኤክስፐርቶቹን በቬኔሲያ ፓላስ ሰብስቦ ሰፊ ጥናት ካካሄደ በኋላ፤ አንድ ሚሊዮን ሰባት መቶ ሺህ ቶን የሚመዝኑ ልዩ ልዩ ለምድርና ለአየር ኃይል የሚያገለግሉ የጦር መሣሪያዎች፤ እንዲሁም የነዳጅ ዘይትና ከሰል የሚያስፈልጉት መሆኑን ዘርዝሮ አቀረበ። ከቡር ፉዩረር ይህንን ሁሉ ጥያቄ

ሲመለከት እጅግ ተገረመ። ከዚህም በላይ በጣም አስደናቂ ሆኖ ያገኘው፣ እነዚህን ሁሉ መሣሪያዎች ከጀርመን ወደ ጣልያን አገር ጭኖ ለመላክ፣ ዐሥራ ሰባት ሺህ የባቡር ፉርጉዎች ያስፈልጋሉ ተብሎ የተገለጸው ነው። በዚህ ሰዓት፣ ከዱቼ ጋር መቀያየሙ ወይም መራራቁ ለሂትለር ጠቃሚው እንዳልሆነ ተገነዘበ። ሙሶሊኒ ያመለከተው፣ እንደኛ/ በአሁኑ ሰዓት ለጦርነቱ ስላልተዘጋጀሁ ጊዜ ይሰጠኝ፣ ወይም ደግሞ የሚያስፈልጉኝን መሣሪያዎች እርስዎ ካሟሉልኝ፣ ዝግጁ እሆናለሁ ለማለት እንጂ፣ የሮምንና የበርሊንን አክስ የማፍረስ ዝንባሌ ለማሳየት አይደለም። ስለዚህ፣ የተሻለው መንገድ ሙሶሊኒ በራሱ አቅም ዝግጅቱን እስኪያሟላ ድረስ፣ ጣልያን ለጊዜው "ኒውትራል" ሆና እንድትቀይ መፍቀድ ነው ተብሎ በናዚ ምክር ቤት ተወሰነ። አማቹ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር ቺያኖ እና ሌሎቹም የካቢኔ አባሎች በሙሉ፣ ጣልያን በጦርነቱ ውስጥ ከጀርመን ጐን ሳትሰለፍ "ኒውትራል" ሆና ትቀያለች ስለተባለ፣ ከመጠን በላይ ተደስተዋል። ይህ የኒውትራል አቋም የሚሰነብተው ለስንት ጊዜ ነው? .... ሙሶሊኒ፣ ቢያንስ ለሚቀጥሉት ሁለት ዓመታት ሊሆን ይችላል ብሎ አስቧል። ነገር ግን፣ የሂትለር እርምጃ እስከዛሬ እንደታየው እየፈጠነ ከሄደ፣ ዱቼ እንደ ተመኘው ለሁለት ዓመታት ይቆያል ለማለት እጅግ የሚያጠራጥር ነበር።

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፣ ከመስከረም 1939 ዓ.ም እስከ ግንቦት 1940 ዓ.ም ድረስ፣ ባለፉት ስምንት ወራት ውስጥ፣ ከማህል አውሮፓ ፖላንድ፣ ከሰሜን ዴንማርክና ኖርዌይ፣ ከምዕራብ ቤልጊክ ሆላንድና ሉክሳምቡርግ ከተያዙ በኋላ፣ አዶልፍ ሂትለር ጦሩን በፈረንሣይ ላይ ሲደግን፣ ሙሶሊኒ ኒውትራልነቱን ለመሰረዝና እኔም ከፊዩረር ጋር አለሁ ለማለት ብድግ አለ። በዚህ ጊዜ ከአማቹ ከቺያኖ ጀምሮ መላው የካቢኔ ሚኒስትሮችና መላው የጦር ከፍተኛ መኰንኖች፣ ጣልያን ዛሬ ባላት አቅምና የጦር ድርጅት፣ ከጀርመን ጋር የዓለም ጦርነት ውስጥ ከመግባት፣ ኒውትራልነቷን ጠብቃ መቆየት ይጠቅማታል ብለው ብርቱ ማሳሰቢያ አቅርበው ነበር። ከእነዚህም በላይ፣ የዓለም ታላላቅ መሪዎች፣ የአሜሪካ ፕሬዚዳንት ሩዝቬልት፣ የእንግሊዝ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል፣ የፈረንሣይ ፕሬዚዳንት ፖል ሬይኖ ለሙሶሊኒ በላኳቸው ቴሌግራሞች፣ ጣልያን ጦርነቱ ውስጥ ሳትገባ በኒውትራልነቷ እንድትቀጥል አጥብቀው እንደ ጠየቁ ታውቋል። ይሁን እንጂ፣ ቤኒቶ ሙሶሊኒ ይህ ሁሉ ትክክል መስሎ አልታየውም። " ... እኔ የምመራት ታላቋ ጣልያን፣ እስከዛሬ ድረስ ከጀርመን ጋር ተሰልፋ ሳትዋጋ በመቅረቷ፣ ክብሯ ተነክቷል። አሁንም በቶሎ ከፊዩረር ጋር ሳንሰለፍ ብንዘገይ፣ የማይታረም ጥፋት ላይ እንወድቃለን ... " ብሎ የራሱን የዲክታተር ውሳኔ ሰጠ። በዚህ መሠረት ሰኔ 10 ቀን 1940 ዓ.ም በሮም የሚገኙት የፈረንሣይና የእንግሊዝ አምባሳደሮች፣ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ ቢሮ ተጠርተው፣ የጦርነት መግለጫ ሲሰጣቸው፣ ጋሌአስ ቺያኖ የባሕር ኃይል የጦር መኰንን ልብስ ለብሶ ነበር። በዚሁ ጊዜ፣ በዕድሜ የገፋውና በኤክስፒሪያንስ የበለጸገው የታወቀው የፈረንሣይ አምባሳደር አንድሬ ፍራንስዋ ፖንሴ (Andre Francois Poncet) የውጭ ጉዳይ ሚኒስትሩ የለበሰውን የጦር ዩኒፎርም " እንዴት ይቀበልዎታል? " የሚል አድናቆት ከገለጸለት በኋላ፣ " ... ወጣት ስለሆኑ፣ የምመክረዎ እንዳይገደሉ ራስዎን ይጠብቁ ብዬ ነው ... " ብሎት ከቢሮው ወጣ። ይህ ፈረንሣዩ ዲፕሎማት የተናገረው ቃል ትንቢት ሆኖ ሦስት ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ሲደርስ ታይቷል። የዱቼ አማች ጋሌአሶ ቺያኖ፣ ጣልያን ከጀርመን ጋር ተሰልፋ የምታደርገውን ጦርነት ማቋረጥ አለባት የሚል አቋም በመያዙ፣ ከሌሎቹ ተመሳሳይ ሐሳብ ከነበራቸው ከነ ጄኔራል ኤሚሊዮ ደ-ቦኖ ጋር በሙሶሊኒ ፍርድ፣ በተወለደ በዐርባ አንድ ዓመቱ በጥይት ተደብድቦ ተገደለ።

# ምዕራፍ ፲

## ፈረንሣይ በቶሎ ወደቀች፤ እንግሊዝ በቆራጥነት ብቻዋን !

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፤ እ.ኤ.አ ግንቦት 10 ቀን 1940 ዓ.ም፤ ሂትለር፤ የሆላንድን፣ የቤልጂክንና የሉክሰአምቡርግን ኒውትራልነት ጥሶ ከወረራቸው በኋላ፤ የአጥቂ ጦሩን ወደ ፈረንሣይ ሲያሻግር፤ በእንግሊዝ አገር የካቢኔ ለውጥ ተደረገ። ካለፉት ሦስት ዓመታት ጀምሮ (1937-1940) ኮንሴርቫተሩ ኔቪል ቻምበርሌን ሲመራው የቆየው መንግሥት፤ በተለይ በኢትዮጵያና በቼኮስሎቫኪያ ጉዳይ፤ ለሙሶሊኒ እና ለሂትለር ደካማነት በማሳየቱ በብዙ ሲወቀስ ከርሞ ነበር። አሁን ደግሞ የዓለም ጦርነት ከተጀመረ በኋላ፤ ኔቪል ቻምበርሌን የሚያሳየው መንፈስና ሁኔታ፤ ታላቋ ብሪታንያን ወደ ውርደት አቅጣጫ የሚመራ ይሆናል በሚል ስጋት፤ የኮንሴርቫቲፍ ፓርቲ አባሎች በሙሉ፤ አዲስ ጠቅላይ ሚኒስትር መሾም አስፈላጊ መሆኑን ተስማሙበት። ካሉትም የፖለቲካ ሰዎች መካከል ዊንስተን ቸርችል የተሻለ ሆኖ በመገኘቱ፤ የእንግሊዝ ንጉሥ ጆርጅ ስድስተኛ ወዲያውኑ ጠርተው አዲሱን ካቢኔ እንዲያቋቁም ጠየቁት። ዊንስተን፤ ቀደም ሲል ቻምበርሌን በሚያሳየው የአመራር ደካማነት ምክንያት፤ ምናልባት እኔ ሳላስፈልጋቸው አልቀርም በማለት፤ ውስጥ ውስጡን ሲዘጋጅ የቆየ በመሆኑ፤ ቤኪንግሃም ቤተመንግሥት ተጠርቶ ይህ ከፍተኛ ኃላፊነት ሲሰጠው፤ ለመቀበል አላመነታም።

ዊንስተን ቸርችል፤ በዚህ በግንቦት 10 ቀን 1940 ዓ.ም፤ ፓርለማው እስኪያፀድቅለት ድረስ እጩ ጠቅላይ ሚኒስትር ተብሎ ከባኪንግሃም ቤተመንግሥት ሲመለስ፤ የሠራተኛው ክፍል የፖለቲካ ፓርቲ መሪ የሆነው ክሊመንት አትሊና፤ የሊበራሉ አርሺባልድ ሰንክሌር፤ (Clement Attlee and Archibald Sinclair) በዚህ የመከራ ዘመን በምታቋቁመው ካቢኔ፤ ያንተን መሪነት ተቀብለን ልንካፈል እንችላለን ብለው ቃል ሰጡት። እነዚህ የተቀዋሚዎቹ ፓርቲዎች ከጥቂት ሳምንታት በፊት፤ በኔቪል ቻምበርሌን ካቢኔ ውስጥ እንዲካፈሉ ተጠይቀው አንቀበልም ካሉ በኋላ፤ አሁን እንዲህ በቶሎ ለቸርችል ዝግጁ ሆነው በመገኘታቸው፤ ለአዲሱ ጠቅላይ ሚኒስትር ወሰን የሌለው ደስታ ፈጠረለት። በዚህ አኳኋን፤ አዲሱ ካቢኔ በታላላቆቹ የፖለቲካ ፓርቲዎች በሙሉ የተደገፈ ስለሆነ፤ ዊንስተን ስፔንሰር ቸርችል ሹመቱ እንዲፀድቅለት ሚኒስትሮቹን አሰልፎ ፓርለማ የቀረበው፤ በተደላደለና በጠንካረ መንፈስ ነበር። በፓርለማው ሰገነት ላይ ቆሞ ለሕዝቡ እንደራሴዎች ባደረገው ንግግር የገለጻቸው ከልብ የመነጩ አስተያየቶች፤ በቸርችል ታሪክ ውስጥ ዘወትር እየታሰቡ እንዲኖሩ ተመዝግበውለታል።

" ... ዛሬ ከፊታችሁ ቆሜ የምነግራችሁ፤ ከሁለት ቀናት በፊት ባቋቋምኩት መንግሥት ውስጥ፤ ተካፋይ ለመሆንና አብረውኝ ለመዝመት ዝግጁ ለሆኑት የሥራ ጓደኞቼ የተናገርኩትን ነው። የመጣብንን እጅግ አስፈሪና ጉደኛ የሆነ ጠላት ለመዋጋት፤ ሥቃዩን በጥንካሬ ከመቀበል፤ ደሜን ከማፍሰስ፤ እንባዬንና ላቤን ከማንጠፍጠፍ በስተቀር፤ ለአገሬ ሌላ የማበረክትላት የተሻለ ነገር

የለኝም ብያለሁ። ይሁንና፣ ዛሬ እናንተ ደግሞ ዓላማህ ምንድን ነው? ብላችሁ ብትጠይቁኝ፣ በምድር፣ በአየርና በባሕር ከጠላታችን ጋር መዋጋት ነው እላችኋለሁ። ቀጥላችሁም፣ ግብህ ምንድን ነው? ብትሉኝ፣ ለዚህም መልሴ አጭር ነው። ግቤ፣ " ድል ማድረግ ብቻ ነው። " ለአገራችን ጠላታችንን ድል ከማድረግ በስተቀር ሌላ ምርጫ የለንም። ለዚህም፣ ሁላችንም አብረን መቆም፣ አብረን መጋፈጥ፣ አብረን መስዋዕት መሆንና አብረን ድልን መጐናጸፍ አለብን.... " ሲል መግለጫውን ደመደመ።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ አዲሱ የዊንስተን ቸርችል ካቢኔ በቀየሰው ዓላማና ለግቡም ባለው ቁራጥነት፣ የመላውን የሕዝብ እንደራሴዎችንና የፖለቲካ መሪዎችን ድጋፍና ዕምነት ስለአገኘ፣ የጠነከረ መንግሥት ሆኖ ለመቋቋም ችሏል። በገለጸው አቋም መሠረት፣ ጠላትን ወግቶ ድል ከማድረግና ከመደምሰስ በስተቀር፣ ሌላ መንገድ እንደማይከተል አረጋግጦ ጉዞውን ሲቀጥል፣ የቃል ኪዳን ጓደኛው በሆነው በፈረንሣይ መንግሥት በኩል የደረሰው ሁኔታ እጅግ የሚያሳዝንና እጅግም የሚያሳስብ ሆነበት። ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፣ አዶልፍ ሂትለር፣ የኒውትራል አቋም ይዘው የነበሩትን አገሮች ቤልጌከን፣ ሆላንድንና ሉክሳምቡርግን ከወረረ በኋላ፣ ወደ ፈረንሣይ ሲዘምት፣ ከግንቦት 14 ቀን እስከ ግንቦት 16 ቀን 1940 ዓ.ም ድረስ ባሉት ሁለት ቀናት ውስጥ፣ የናዚ ጦር ፈረንሣዮችን እየደመሰሰ፣ ወደ ፓሪስ ያልተጠበቀ ግሥጋሴ አደረገ። በዚህ ግንባር ላይ የፈረንሣይ ጦር ዋና አዛዥ የሆነው ጄኔራል ጋምለን፣ (Gamelin) የጀርመንን ኃይል ለመቋቋም የሚያስችል አቅም አለመኖሩን በማየት ከ24 ሰዓት በኋላ፣ ዋናዋ ከተማ ፓሪስ በጠላት እንደምትያዝ፣ ለመንግሥቱ አስታወቀ። በዚያን ጊዜ፣ ከሦስት ወራት በፊት የፈረንሣይ ጠቅላይ ሚኒስትር በመባል በፓርለማው የአንድ ድምፅ ብልጫ ብቻ ይዞ መንግሥቱን የሚመራው ፖል ሬይኖ (Paul Reynaud) ጀርመኖች ፓሪስን ከመያዛቸው በፊት ዋና ዋና የሆኑት የመንግሥት ሰነዶች ሁሉ እንዲቃጠሉ ትዕዛዝ ሰጠ። ኋላ ግን እንደታየው፣ የተፈራው በቶሎ አልደረሰም። ጀርመኖቹ በቀጥታ ፓሪስ ከመግባት ይልቅ፣ ከከተማዋ በስተምሥራቅና በስተደቡብ በኩል ወደ ውስጥ እየዘለቁ፣ በቅድሚያ የአካባቢዎቹን አውራጃዎች መያዝ ይሻላል ብለው ወሰኑ። የጠላታቸው ዕቅድ እንደዚህ መሆኑን የፈረንሣይ የጦር አለቆች በመረጃ አግኝተውት ቢሆን ኖሮ፣ ምናልባትም የኬ-ዶርሰይን (Quai D' orsay) መዛግብት ከማቃጠል ወደ ሌላ ቦታ አዛውሮ ለማዳን ሳይቻል አይቀርም ነበር። ለማናቸውም ፓሪስ ጠላት ሳይዛት ከሦስት ሳምንታት በላይ መቆየት አልቻለችም። የፈረደበት የፖል ሬይኖ መንግሥት ሰኔ 10 ቀን 1940 ዓ.ም፣ ዱቼ ሙሶሊኒ የሂትለር ወገን ሆኖ በደቡብ ፈረንሣይ በኩል ጦርነት ሲከፍትበት፣ ወዲያውኑ ፓሪስ ውጊያ የማይደረግባት ነፃ ከተማ መሆኗን መግለጫ ሰጥቶ፣ በደቡብ ምሥራቅ አቅጣጫ ወደሚገኘው ቦርዶ (Bordeaux) ወደተባለው ከተማ ሸሸ። የፈረንሣይ መንግሥት ቦርዶ ደርሶ ጊዜያዊ ቦታውን በያዘ በሁለተኛው ቀን፣ ሰኔ 14/1940 ዓ.ም፣ የናዚ ጦር እየሸለለ ነፃ ከተማ ተብላ ጠላቷን ለመቀበል በሯን ከፍታ የጠበቀችውን ፓሪስን በእጁ አደረገ። ፉዩረር ሂትለርም ከደስታው ብዛት ፓሪስ በተያዘች በሦስተኛው ቀን በጥድፊያ ሄዶ፣ ይህችን ውብና ታሪካዊ የሆነች ከተማ በሕይወቱ ለመጀመሪያ ጊዜ የአንድ ቀን ጉብኝት በማድረግ አደነቃት።

በሰሜን አውሮፓ በኩል የተሰለፈው ትልቁ የፈረንሣይ ጦር፣ አርባ ቀናት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ እንደዚህ ተንኮታኩቶ ድል እንደሚሆን የሚያስብ አልነበረም። የናዚ ኃይል፣ ምንም እንኳ በመሣሪያም ዓይነት ሆነ በሠራዊት ብዛት ብልጫ እንዳለው አስቀድሞ የታወቀ ቢሆንም፣ እንደዚህ ባጭር ጊዜ ውስጥ ፓሪስ ገብቶ

የፈረንሣይን ማንቁርት መያዙ፣ ለራሱ ለሂትለርም ከሚጠብቀው በላይ ስለሆነበት፣ እጅግ አስደንቆታል። ካለፉት ሦስት ወራት ጀምሮ በአንድ ድምፅ ድጋፍ ብቻ እየተንገዳገደ የቆየው የፈረንሣይ መንግሥት፣ ሰኔ 12 ቀን ፓሪስን አስረክቦ ወደ ቦርዶ ከተዛወረ በኋላ፣ ዋና ዓላማው ከእንግሊዝ ጠቅላይ ሚኒስትር ከዊንስተን ቸርችል ጋር በቅርብ እየተባበረ ከጠላት ጋር ውጊያውን ለመቀጠል ነበር። ነገር ግን፣ በፓርለማው ካሉት የፖለቲካ ፓርቲዎች መካከል አብዛኞዎቹ፣ ፈረንሣይ ፍጹም ድል እንደሆነች አድርገው በመቁጠር፣ ከናዚ መንግሥት ጋር የጦርነት ማቆሚያ ውል መደራደር ይሻላል የሚል አቋም በመያዛቸው፣ ፖል ሬይኖ ያችን የነበረችውን የአንድ ድምፅ መንግሥት ሥልጣን ለቅቆ ወጣ።

ሰኔ 16 ቀን 1940 ዓ.ም፣ በፖል ሬይኖ ምትክ፣ በመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ዘመን በፈረንሣይ አገር ቬርደን ላይ (Verdun) በተደረገው ውጊያ፣ ጀርመንን ድል በማድረግ የታወቀው ጀግና ማሬሻል ፊሊፕ ፔተን፣ (Philippe Petain) አዲስ መንግሥት እንዲያቋቁም የፓርለማውን ሙሉ ድጋፍ አገኘ። በዚያን ጊዜ፣ በዓለም ላይ እጅግ አስገራሚ ሆኖ የታየው፣ ይህ ባለፈው ታሪኩ ስመጥር የሆነው የጦር መሪ፣ ፈረንሣይ ባላት አቅም ሁሉ ከእንግሊዝ ጋር ሆና፣ እስከመጨረሻው ድረስ ከጠላት ጋር መዋጋቷን እንድትቀጥል በማድረግ ፋንታ፣ ከሂትለር ውርደትን ተቀብሎ ጦርነቱን ለማቆምና ከዚያም አልፎ፣ በናዚ መንግሥት የበላይ መሪነት ተወስኖ የተሰጠውን የፈረንሣይ ግዛት ለማስተዳደር መስማማቱ ነበር። ማሬሻል ፔተን፣ በዚህ በወሰደው እርምጃ የአገሩን ክብር ከማዋረዱም በላይ ፈረንሣዮችን ብቻ ሳይሆን፣ የታላቋ ብሪታንያንና እንዲሁም የአውሮፓን ሕዝቦች በማሳዘኑ፣ የቪሺ (Vichy) ከሀዲ መንግሥት እየተባለ በታሪክ ላይ ሲወገዝ ይኖራል።

ፈረንሣይን ያዋረዳት የናዚ መንግሥት ብቻ አልነበረም። የፋሽስቱ መሪ ሙሶሊኒም እንደአቅሙ፣ ሰኔ 10 ቀን 1940 ዓ.ም በፈረንሣይ ላይ ጦር መምዘዙን አስታውቆ ወታደሮቹን ወደ ደቡብ ግንባር ከላከ ከአሥር ቀናት በኋላ፣ ድል አድራጊው ፊዩረር ከማሬሻል ፔተን ጋር የጦርነት ማቆሚያ ስምምነት ለማድረግ መዘጋጀቱ ተገለጸ። በዚህ ጊዜ፣ ጣልያንም አብራ ከኀያሯ ከጀርመን ጋር በአሸናፊነት የፊርማው ተካፋይ መሆን አለባት ብሎ ጀግናው ዱቼ ጠይቆ ነበር። አዶልፍ ግን፣ ቤኒቶ ባልሠራው ጀብዱ በመጨረሻው ሰዓት ብቅ ብሎ የጀርመን ክብር ተካፋይ እንዲሆን አልፈለገም። ይሁን እንጂ፣ ጣልያን ተዋግቼ ድል አግኝቼበታለሁ በምትለው በደቡብ ፈረንሣይ ግንባር፣ ከቪሺው መንግሥት መሪ ከማሬሻል ፔተን ጋር መደራደር ትችላለች ብሎ ፈቀደለት።

ቀደም ሲል፣ ሙሶሊኒ የሂትለር ግብረአበር ሆኖ በጦርነቱ ውስጥ ከመግባት ይልቅ፣ "ኒውትራል" ሆኖ እንዲቆይ፣ የፈረንሣይ መንግሥት አጥብቆ ስለፈለገ፣ በአፍሪካ ውስጥ ካሉት ግዛቶቹ፣ 1ኛ/ ጂቡቲንና ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ ያለውን የባቡር መስመር ለፋሽስት መንግሥት ለማስረከብ፣ 2ኛ/ ከደቡብ ሊቢያ እስከ ጊኔ ድረስ ያለውን የባሕር ወሽመጥ ሰፊ ግዛት ለመስጠት፣ 3ኛ/ የቱኒዚያን አውራጃዎች ለጣልያን በሚመች መልክ አከፋፍሎ፣ ለሙሶሊኒ ጉቦ ለመስጠት አዘጋጅቶ ነበር። ፋሽስቱ ዲክታተር ግን፣ ይህ ሁሉ ጠቃሚ አይደለም በማለት፣ አልተቀበለም። በመሠረቱ የዱቼ ዋና ዓላማ፣ ጦርነቱ ከተጀመረ ዓመት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ ፊዩረር ብዙ ድል እያገኘ ስለመጣ፣ ጊዜው ሳያልፍበት እሱም ከእሱ ጐን ቆሞ በዓለም ላይ ድል አድራጊ መስሎ ለመታየት ስለሆነ፣ ደካማው የፈረንሣይ መንግሥት ያቀረበለትን የመለማመጫ ጉቦ ከቁም ነገር አልቆጠረውም።

ከሰኔ 11 ቀን 1940 ዓ.ም ጀምሮ፣ በደቡብ ፈረንሣይ በኩል የዘመተው የሙሶሊኒ ጦር፣ የኒስ (Nice) ከተማንና በአካባቢዎቹ የሚገኙትን ሁሉ ለመያዝ ባደረገው ጦርነት፣ ፈረንሣዮች በጀግንነት ተዋግተው ቁጥራቸው ከሰባት ሺህ በላይ (7000) የሆኑትን የፋሽስት ወታደሮች ከገደሉ በኋላ፣ ባልታወቀ ምክንያት ወደ ኋላ በማፈግፈጋቸው፣ በዚህ ግንባር የተደረገው ጦርነት ድሉ የጣልያን ነው ተብሎ ተነገረ። የሙሶሊኒም መንግሥት ያ ሁሉ ወታደር ካለቀበት በኋላ፣ ፈረንሣዮቹን ድል አድርጌ አባርሬያለሁ በማለት፣ የፕሮፖጋንዳ ፋከራ እያደረገ፣ ከማሬሻል ፔተን ጋር የጦር ማቆሚያ ስምምነት ለመፈራረም ዝግጁ መሆኑን አስታወቀ። በዚህ መሠረት ሰኔ 24 ቀን 1940 ዓ.ም፣ በሮም ከተማ በፋሽስትና በፈረንሣይ መካከል የጦርነት ማቆሚያ ስምምነት ቢደረግም፣ የዱቼ መንግሥት ይህን ያህል ጠቃሚ የሆኑ ነገሮችን አላገኘም። በጣልያን አገር ብዙ ጭብጨባ የተደረገለት የድል አድራጊ ውል የሚያመለክተው፣ 1ኛ/ በጣልያንና በፈረንሣይ ወሰን መካከል ጦር የማይሰፍርበት አምሳ ኪሎ ሜትር ስፋት ያለው ዞን እንዲከለል መወሰኑ ሲሆን፣ 2ኛው ደግሞ፣ ቀደም ሲል በፖል ሬይኖ ይመራ የነበረው የፈረንሣይ መንግሥት የተስማማበትን፣ የጂቡቲን ወደብና ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ ያለውን የባቡር መስመር የፋሽስት መንግሥት እንዲጠቀምበት መደረጉ ነው። ከዚህ ሌላ ዱቼ ሙሶሊኒን የሚያስፎክር ጆብዱ አልነበረም።

ከመጋቢት 22 ቀን 1940 ዓ.ም ጀምሮ፣ ፈረንሣይ በናዚ ጦር ድል እስከሆነችበት እስከ ሰኔ 16 ቀን 1940 ዓ.ም ድረስ፣ መንግሥቱን ይመራ የነበረው ፖል ሬይኖ ሥልጣኑን ሲለቅ፣ ለአገሩ አለኝታ መሆን ለቻለ ለአንድ ትልቅ ሰው ዕድል ከፍቶ በመሄዱ፣ በታሪክ ላይ ሲጠቀስ የሚኖር ስለሆነ፣ የደረሰውን ሁኔታ በመጠኑም ቢሆን ማብራራቱ የሚጠቅም ይሆናል። ይኸውም፣ ኮሎኔል ሻርል ደጎል (Charles de Gaulle) የተባለውን የጦር መኰንን በውትድርና ሞያውና በብልህነቱ ከሁሉም የበለጠ ሆኖ ስለአገኘው፣

1ኛ/ ሰኔ 1 ቀን 1940 ዓ.ም ቀደም ሲል በጦር ምክር ቤት ተወስኖለት የነበረውን የብሪጋድየር ጄኔራልነት ማዕረግ፣ ቢሮክራሲው ተፋጥኖ በቶሎ እንዲሰጠው አስደረገ።

2ኛ/ ሰኔ 5 ቀን 1940 ዓ.ም የመከላከያ ሚኒስቴር ረዳት ሚኒስትር አድርጐ በመሾም፣ ስለ ጦርነቱ አመራር በሎንደን ከቸርችል መንግሥት ዘንድ የፈረንሣይ ዋና ሊዩዞን ሆኖ እንዲሠራ መደበው።

ጄኔራል ደጎል ይህን ከፍተኛ ኃላፊነት ተቀብሎ በሎንደን ለአሥር ቀናት ያህል ሥራውን በማካሄድ ላይ እንዳለ፣ የፖል ሬይኖ ካቢኔ ወድቆ በምትኩ አዲስ የተቋቋመው የማሬሻል ፔተን መንግሥት፣ ከሂትለር ጋር ፈረንሣይን የሚያዋርድ ድርድር አድርጐ የጦርነት ማቆሚያ ስምምነት ሲፈራረም፣ ሊዩዞን አፈሰሩ፣ አልቀበልም ብሎ በፅኑ ተቃወመ። ሻርል ደጎል በዚህ ቆራጥ በሆነው አቋሙ፣ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል እና ካቢኔው ስለደገፈው፣ ሰኔ 18 ቀን 1940 ዓ.ም በሎንደን ቢ.ቢ.ሲ ራዲዮ ቀርቦ ለመላው የፈረንሣይ ሕዝብ በታሪክ ላይ ተቀርጾ የሚኖር ከፍ ያለ ንግግር አደረገ። " ... ፈረንሣይ በአንድ ግንባር ላይ ከጠላቷ ጋር ባደረገችው ውጊያ ተሸንፋለች ቢባልም፣ ዛሬ በመካሄድ ላይ ባለው የዓለም ጦርነት ላይ ድል አልሆነችም። የዓለም ጦርነት ተጀመረ እንጂ አላለቀም። ፈረንሣዮች ወገኖቼ ! እመኑኝ ! የምነግራችሁ የማውቀውንና ትክክለኛውን ነው። ፈረንሣይ ምንም አልተነካችም። ዛሬ የደረሰባትን መሸነፍ ነገ በሌላ ትልቅ ድል ትተካዋለች።



እነ ፒየር ላቫል ፈረንሣይን ለሂትለር ሲያስረክቡ፣ ፈረንሣይ አልሞተችም
ነፃ ነች ብሎ እስከ መጨረሻው የተዋጋና ድሉን የተቀዳጀው፣
ፈረንሣዊው የነፃነት አርበኛ ብሪጋድየር ጄኔራል ሻርል ደጐል፣

... ፈረንሣይ ብቻዋን አይደለችም። የቀረው ቢቀር፤ በባሕር ማዶ ግዛቶቿ ላይ ያሏት ኃይሎቿ በቀላሉ የሚገመቱ አይደሉም። ...

ታላቋ ብሪታንያ የባሕሯን ዙሪያ ተቆጣጥራ በመያዝና ለጠላት አላጐነበስም በማለት ጦርነቱን እንደቀጠለች ሁሉ፤ ፈንሣይም ከእሷ ጋር ሆና ተጋድሎዋን መቀጠል ትችላለች። ዛሬ ተስፋ ቆርጠው፤ ለጠላታችን በመንበርከክ ድል ሆነናል ብለው፤ የፈረንሣይን ክብር በማዋረድ ላይ የሚገኙት የጦር መሪዎቻችን፤ እጅግ መሳሳታቸውን ተረድተው ወደ እኛ ካልተመለሱ፤ የሚጠብቃቸው ፍርድ በጣም የከበደ ይሆንባቸዋል። ፈረንሣዮች ወገኖቼ ፤ እኔ ጄኔራል ደጐል፤ ሉንደን ሆኜ የምነግራችሁ፤ የፈረንሣይ ነፃ አውጭ ብሔራዊ ኮሚቴ መቋቋሙንና በሁላችንም አንድነትና ትብብር፤ ከጠላታችን ጋር እስከመጨረሻው ለመዋጋት ቆርጠን መነሳታችንን ነው። ስለዚህ፤ የፈረንሣይ የጦር መኰንኖችና ወታደሮች ሁሉ፤ መሣሪያ የያዛችሁ ወይም የሌላችሁ፤ በኢንዱስትሪ መስክ ወይም በመሣሪያዎች ፋብሪካ፤ መሀንዲሶችና ባለሞያ የሆናችሁ ሁሉ፤ በጠቅላላውም ለነፃነት ትግል በአገር ፍቅር መንፈስ የተነሳሳችሁ ሁሉ፤ ከእኔ ጋር ግንኙነት በማድረግ ለጦርነቱ እንድንደራጅ እጠይቃለሁ። የደረሰ ቢደርስ፤ በምንም ምክንያት የፈረንሣይ የትግል ኃይል አይዳከምም። ሊዳከምም አይችልም ... "

ሻርል ደጐል በቢቢሲ (B.B.C) ራዲዮ ይህን ንግግር በማስተላለፍ የፈረንሣዮችን ያገር ፍቅር መንፈስ ከቀሰቀሰበት ዕለት ጀምሮ፤ " የሰኔ አሥራ ስምንቱ ሰው " (L' Homme Du 18 Juin) የተባለ የአክብሮት መጠሪያ ስለተሰጠው፤ በታሪኩ ላይ ሁልጊዜ ሲጠቀስለት ይኖራል። ደጐል ለፈረንሣይ ወገኖቹ፤ አልሞትንም ተነሱ እንዋጋ የሚል ጥሪ ባቀረበ በአራተኛው ቀን፤ ማሬሻል ፔተንና ረዳቶቹ እነ ፒየር ላቫል፤ የናዚ መንግሥት በሚፈልገው ዓይነት ፈረንሣይን እጅግ አድርጎ የሚያዋርደውን የጦር ማቆሚያ ስምምነት ለመፈረም መዘጋጀታቸውን አስታወቁ። በመጀመሪያው የዓለም ጦርነት ፍጻሜ ላይ፤ ጀርመን ድል ሆና የጦር ማቆሚያ ስምምነት ለመፈረም በኅዳር 11 ቀን 1918 ዓ.ም በቀረበች ጊዜ፤ ፈረንሣይ የፈጸመችባትን በደልና ያደረሰችባትን ውርደት አንድ ቀን ለመበቀል የአዶልፍ ሂትለር ዋና ምኞት ሆኖ የቆየ ጉዳይ ነበር። በዚህ ቂም መሠረት፤ ከሀያ አራት ዓመታት በኋላ፤ ሰኔ 22 ቀን 1940 ዓ.ም፤ ፈረንሣይ በተራዋ በጦር ሜዳ መሸነፏንና የናዚንም መንግሥት የበላይነት ማወቋን አጐንብሳ የምትፈርመው፤ ኅዳር 11 ቀን 1918 ዓ.ም ጀርመን ተንበርክካ በፈረመችበት ታሪካዊ በሆነው ልዩ የባቡር ፉርጐን ውስጥ እንዲሆን ተደረገ። ይህ ፉርጐን ካለፉት 24 ዓመታት ጀምሮ ለፈረንሣይ የድል አድራጊነት ታሪክ ነው ተብሎ በሚዚየም ውስጥ በክብር ተቀምጦ ይኖር ነበር። ነገር ግን፤ የአዶልፍ ሂትለር ዋና ዓላማ፤ ፈረንሣይ በሰፈረችው ቁና መሰፈር አለባት የሚል ስለሆነ፤ ይህ ጀርመን ተንበርክካ ኅዳር 11 ቀን 1918 ዓ.ም የፈረመችበት ፉርጐን ከሚዚየም ወጥቶ ፈረንሣይም በተራዋ ሰኔ 22 ቀን 1940 ዓ.ም ተንበርክካ ድል መሆኗን እንድትፈርምበት አስደረገ። ፉዩረር፤ በዚህ በደረሰው አጋጣሚ ታሪክ እጅግ ከመደሰቱ የተነሳ፤ እሱ ራሱ በቦታው በመገኘት፤ የአሸናፊውና የተሸናፊው ወገኖች ውሉን ለመፈራረም ፉርጐኑ ከተዘጋጀበት ሥፍራ ሲደርሱ፤ እያንዳንዳቸውን የእጅ ሰላምታ ከሰጣቸው በኋላ፤ "በሉ እንግዲህ ታሪካዊ ሆኖ ለዘለዓለሙ የሚኖረውን ሥራችሁን አከናውኑ" በሚል ቃል ትቷቸው ወደመጣበት ተመለሰ። በዚህ አኳኋን ፈረንሣይ፤ እስከዚህ ጊዜ ድረስ በታሪኳ ደርሶባት የማያውቀውን ውርደት አሜን ብላ ከተቀበለች በኋላ፤ ከግዛቷ በተወሰነ ክልል ውስጥ፤ ቪሺ በተባለው ከተማ የመተዳደሪያ መንግሥቷን እንዲያቋቁምላት የተጠየቀው ማሬሻል ፔተን፤ ታማኝነቱን ለሂትለር እያረጋገጠ

መኖር ሲጀምር፣ ሻርል ደጎል ደግሞ፣ የነፃይቷ ፈረንሣይ መሪ ነኝ ብሎ፣ ከጠላት ጋር ለመዋጋት ዝግጅቱን ቀጠለ።

ጄኔራሉ በወሰደው እርምጃ፣ ፊዩረር እጅግ አድርጎ ስለተቆጣ፣ የቪሺ መንግሥት ልዩ የጦር ፍርድ ቤት በማቋቋም፣ ሐምሌ 7 ቀን 1940 ዓ.ም፣ ደጎል የፈረንሣይ ዜግነቱ ተገፍፎ፣ የሞት ቅጣት እንዲፈረድበት አስደረገ። ይህ አሳዛኝ ውሳኔ የፈረንሣይን ነፃ አውጭ መሪ አላሳሰበም። በዚያን ጊዜ የሻርል ደጎል ትልቁ ችግር፣ የቸርችል መንግሥት የነፃይቱ ፈረንሣይ መሪ መሆኑን በይፋ አውቆለት፣ የሚያስፈልገውን እርዳታ እንዲሰጠውና ከእንግሊዝ ጐን ተሰልፎ ውጊያውን ለመቀጠል ነበር። ዊንስተን ደግሞ፣ ሰውየው ያሳየውን ቆራጥነትና ያለውን የጦር ስልት ችሎታ ቢያደንቅም፣

1ኛ/ የጄኔራልነቱ ኢክስፒሪያንስ በሳምንታት ዕድሜ የሚቆጠር በመሆኑ፣ የነፃይቷ ፈረንሣይ መሪነቱን ሕዝቡ ላይቀበለው ይችል ይሆናል በማለት፣

2ኛ/ ደጎል በተፈጥሮው ዕብሪተኛ የሆነ መንፈስ ስለአለው፣ እኛንም ሊያስቸግረን ይችላል በሚል ሥጋት፣ የጠየቀውን ሁሉ በቶሎ መፈጸም አስፈላጊ ሆኖ አልታየውም።

በእነዚህ ከዚህ በላይ በተደረደሩት ምክንያቶች፣ ጄኔራል ደጎል የነፃይቷ ፈረንሣይ መሪ ሆኖ ትግሉን ለመቀጠል ካወጀበት ከሰኔ 18 ቀን 1940 ዓ.ም ጀምሮ፣ የታላቋ ብሪታንያን እርዳታና ሙሉ ዕውቅና ለማግኘት ለሁለት ወራት ያህል ሲቸገር ከቆየ በኋላ፣ በመጨረሻው ከነሐሴ ወር አጋማሽ ጀምሮ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የጠየቀውን ሁሉ ፈጸመለት። የነፃይቱ ፈረንሣይ መምሪያ ተብሎ በሎንዶን ለተቋቋመው ጽሕፈት ቤት እና፣ የሚያስፈልጉትንም ሠራተኞች ለመቅጠር፣ የእንግሊዝ መንግሥት በጀቱን መደበለት። እንዲሁም ከነሐሴ 16 ቀን ጀምሮ በቢ.ቢ.ሲ. ራዲዮ " ፈረንሣዮች ከፈረንሣዮች ጋር " የሚወያዩበት የተወሰነ የዕለት ፕሮግራም ለማካሄድ ተፈቀደለት።

የሰኔ 18ቱ ሰው፣ ጣጣው በዚህ ብቻ የሚፈታ አልነበረም። የሁለተኛው የዓለም ጦርነት እየተፋፋመ በሄደበት ሰዓት፣ የአሜሪካና የመስኮብ መሪዎች፣ ፈረንሣይ ያንን ሁሉ ውርደት ከተቀበለች በኋላ፣ ከታላላቆቹ መንግሥታት ጋር አራተኛ አባል ሆና ስለ ጦርነቱ አካሄድ ለመመካከርና የውሳኔ ተካፋይ ለመሆን አይገባትም የሚል አቋም ያዙ። ከዚህም በላይ ትናንት የብሪጋድየር ጄኔራልነት ማዕረግ ያገኘውን ሻርል ደጎልን የነፃይቷ ፈረንሣይ መሪ አድርገው ለመቀበል አልፈለጉም። ደጎል ደግሞ በበኩሉ፣ ማንንም ሳይጠይቀው ከሐሳቡ አንቅቶ ይህንን የነፃይቷን ፈረንሣይ ድርጅት ካቋቋመ በኋላ፣ የፈረንሣይ ሕዝብ በአገር ፍቅር ስሜት ተቀስቅሶ፣ ወታደሩም ሆነ ሲቪሉ፣ ከናዚ ጋር የተባበረውን የቪሺን መንግሥት እየከዳ ምን ያህል ጠላቱን ለመውጋት እንደተዘጋጀ በማስገንዘብ፣ ፈረንሣይ ከታላላቆቹ መንግሥታት ከእንግሊዝ፣ ከአሜሪካና ከመስኮብ ጋር በእኩል ደረጃ የዓለም ጉዳይ ተካፋይ መሆን አለባት ብሎ፣ በጠንከረ መንፈስ ታገለ።

ይሁን እንጂ በተለይ አሜሪካኖች፣ በመጠኑም እንግሊዞች፣ ልዩ ልዩ ተንኮል በመተብተብ፣ ከከሐዲው ከቪሺ መንግሥት ጋር ሲተባበሩ የቆዩትን አድሚራል ዳርላንና ጄኔራል ጂሮ (Admiral Darlan, General Giraud) የተባሉትን

የባሕርና የምድር ጦር መኰንኖች በማዘጋጀት፣ የሰኔ 18ቱን ሰው ፈንቅለው ለመጣል አስበው ነበር። ነገር ግን፣ ሻርል ደጎል እጅግ ብልህና ቀራጥ ከመሆኑም በላይ፣ ብዙ ደጋፊዎች ስለነበሩት፣ መጀመሪያ አድሚራል ዳርላንን በማስገደል፣ ከጥቂት ጊዜ በኋላ ደግሞ፣ ጄኔራል ጂሮንን በማባረር፣ የነፃይቷ ፈረንሣይ መሪነቱን ብቻውን ይዞ ቀጠለ። በመሠረቱ፣ ያ ሁሉ ጠላት ከቦት ለሕይወቱ ሳይሳሳ፣ ይህን የነፃይቷን ፈረንሣይ ድርጅት ያቋቋመ እሱ ብቻውን ሲሆን፣ ሕዝቡም ድጋፉን እየሰጠ ለትግሉ የተሰለፈው የእሱን መሪነት ተቀብሎ ነው። ዛሬ በድንገት ታላላቆቹ መንግሥታት ተነስተው፣ በቦታው ላይ ሌላ ሰው ለመተካት የሚጥሩት በማን ስም ሆነው ነው ? ... በተለይም፣ ከቪሺ ከሐዲ መንግሥት ጋር ተባባሪ ከሆኑት የጦር መኰንኖች መካከል መርጠው የደጎልን ቦታ ለማስያዝ መሞከራቸው ከእነሱ የሚጠበቅ አልነበረም በማለት፣ ከጠላት ጋር ለመዋጋት የተሰለፉት የፈረንሣይ የአገር ፍቅር አርበኞች ሁሉ፣ እጅግ የመረረ ሀዘን ደርሶባቸው ነበር።

ከታላላቆቹ መንግሥታት መካከል፣ ለጄኔራል ደጎል የተሻለ አስተያየት ያለውና ችግሩንም የሚያውቅለት ዊንስተን ቸርችል ብቻ ነበር። እሱም ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው፣ ደጎል በሚያሳየው ኃይለኛ የሆነ ጠባይ ቅሬታ ቢኖረውም፣ ለነፃይቷ ፈረንሣይ ከእሱ የተሻለ መሪ አለመኖሩን ደህና አድርጐ ያውቃል። ፈረንሣይ በጦርነቱ ላይ፣ ጠላቷ ሂትለር ሳይቀር ከፍተኛ መገረም እስኪያድርበት ድረስ፣ በስድስት ሳምንታት ውጊያ መሸነፍ ብቻ ሳይሆን፣ ክብሯን አዋርዳ በመገኘቷ፣ ሀዘኑና ፀፀቱ የፈረንሣዮች ብቻ ሳይሆን፣ የመላው አውሮፓ ሕዝቦች ሆኗል። ይሁን እንጂ፣ ፈረንሣይ ያላት የታሪክና የሥልጣኔ ደረጃ፣ በጥንታዊውም ሆነ በአዲሱ ዘመን፣ በዓለም ጉዳይ የተጫወተችው ሚና የሚዘነጋ አይደለም። ስለዚህም፣ ዛሬ ከናዚ ጋር በምናደርገው ጦርነት ላይ በደረሰባት አደጋ ምክንያት፣ በአራቱ ታላላቅ መንግሥታት መካከል ያላት ቦታ ሊሰረዝባት አይገባም በማለት፣ በያልታ ጉባኤ ላይ ዊንስተን ቸርችል ከሩዝቬልትና ከስታሊን ጋር ተሟግቶ ክብሯን በማስመለስ፣ ለፈረንሣይ ባለውለታዋ ሆኗል። እንዲሁም፣ የሰኔ 18ቱ ሰው ደግሞ በበኩሉ፣ ጽኑና ቀራጥ በሆነው መንፈሱ ያንን ሁሉ መሰናክል አልፎ፣ የነፃይቱ ፈረንሣይ መሪ ሆኖ ነሐሴ 16 ቀን 1944 ዓ.ም በድል አድራጊነት ፓሪስ ሲገባ፣ በፈረንሣይ ሕዝብ ታሪክ ውስጥ እጅግ የተከበረ ቦታ ለማግኘት ችሏል።

## እስከመጨረሻው ያልተበገረ መሪ
## ዊንስተን ቸርችል

ከግንቦት 10 ቀን 1940 ዓ.ም ዓ.ም ጀምሮ ለታላቋ ብሪታንያ አዲስ መንግሥት አቋቁሞ፣ ካቢኔው እንዲጸድቅለት ለፓርለማ ባቀረበ ጊዜ፣ ዊንስተን ቸርችል ባደረገው ንግግር፣ " ... ዋናው ዓላማዬ ከመጣብን ጠላት ጋር ጦርነቱን መቀጠል ነው። ግቤ ደግሞ እስከመጨረሻው ተዋግቼ ድል ማድረግ ነው ... " ብሎ እንደነበረ ይታወሳል። በዚህ ጦርነት ውስጥ የቸርችል መንግሥት ከመነሻው እስከ መጨረሻው የወሰዳቸውን እርምጃዎች ስንመለከት፣ ቃሉን የጠበቀና ግቡንም የመታ ሆኖ እናገኘዋለን።

አዶልፍ ሂትለር፣ ከፍተኛ የሆነ የምድርና የአየር ኃይል ጦር አሰልፎ ፈረንሣይን ለመውረር ሲነሳ፣ ቢያንስ ከአራት እስከ ስድስት ወራት የሚፈጅ ጊዜ እንደሚጠይቀው ተዘጋጅቶ ነበር። ነገር ግን፣ ውጊያው በተጀመረ ስድስት

ሳምንታት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ ፈረንሣዮችን ድል አድርጎ ፓሪስ ሲደርስ፣ እውነት መሆኑን ለማመን እጅግ ተቸገረ። በዚያን ጊዜ ሂትለር ብቻ ሳይሆን፣ ከሂትለር አጠገብ ካሉትም የጦር አለቆች መካከል፣ ፈረንሣይ እንደዚህ አጭር በሆነ ጊዜ ውስጥ ትሸነፋለች ብለው ያሰቡ አልነበሩም። በዚህ በፈረንሣይ ላይ የተገኘው ያልታሰበ ከፍተኛ ውጤት፣ የፊዩረሩንና የረዳቶቹን ሞራል እጅግ ከፍ ያደረገ በመሆኑ፣ እንግሊዝንም ወግቶ ድል ለማድረግ ማበረታቻ አገኙ።

ይህን የተደላደለ መንፈስ በመመርኮዝ፣ የሂትለር የጦር ሚኒስትር ማሬሻል ሔርማን ጎሪንግ (Goering) ታላቋ ብሪታንያን ለመውረር በሦስት ደረጃ የተከፈለ ፕላን ቀየሰ። እነዚህም፣ የመጀመሪያው የጀርመን የአየር ኃይል በእንግሊዝ ግዛት የሚገኙትን የአውሮፕላን ሜዳዎችንና በምድር ተዘጋጅተው የሚጠባበቁትን የጦር አውሮፕላኖች፣ እንደዚሁም የባሕር ኃይል ወደቦችን በቦንብ መደብደብ ሲሆን፣ ሁለተኛው ደግሞ ዋና ዋና ከተሞችንና ኢንዱስትሪዎችን፣ የባቡር ጣቢያዎችንና የመገናኛ መስመሮችን ከጥቅም ውጭ ማድረግ ነበር። እነዚህ በሁለት ደረጃ የተቀየሱት ፕላኖች ከተጠናቀቁ በኋላ፣ በሦስተኛ ደረጃ የሚከናወነው፣ የታላቋ ብሪታንያን ዋና ከተማ ሎንዶንን መያዝና፣ ጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል የጦር ማቆሚያ ስምምነት እንዲጠይቅ ማስገደድ ነው ተብሎ ታቀደ።

በዚህ ፕላን መሠረት፣ ነሐሴ 8 ቀን 1940 ዓ.ም በናዚ በር ከፋችነት የተጀመረውን ጦርነት፣ ባልታሰበ መንገድ የእንግሊዞች የአየር ኃይል እጅግ አድርጎ መመከት ብቻ ሳይሆን በጠላት ላይ ከባድ የሆነ አደጋ በማድረስ ትልቅ ጀብዱ ሠራ። በዚህ አኳኋን፣ ለአሥር ቀናት ያለማቋረጥ በተደረገው ውጊያ፣ ቁጥራቸው ከሰባት መቶ በላይ የሆኑትን የናዚ የጦር አውሮፕላኖች መትቶ በመጣል፣ እንግሊዞች በሰማዩ ጦርነት የበላይነታቸውን አረጋገጡ። የናዚም ጦር በአየር የገጠመው ውጊያ ሳይሳካለት ሲቀር፣ በሎንዶን ከተማ ያሉትን ታላላቅ ሕንፃዎች ብቻ ሳይሆን፣ የሕዝብ መኖሪያዎች የሆኑትን ሁሉ፣ በብዙ ሺህ የሚቆጠር ቶን ቦንብ በማዝነብ፣ የቸርችልን መንግሥት ለማስጨነቅ ሞከረ ነበር። ነገር ግን፣ ምንም እንኳ በትልቋ ደሴት ላይ የናዚ ጦር ያደረሰው ጉዳት በቀላሉ የሚገመት ባይሆንና የሞቱትም ሰዎች ቁጥራቸው ከአሥራ አምስት ሺህ (15.000) በላይ መድረሱ ቢታወቅም፣ የቸርችል መንግሥት ለሂትለር ተዋርዶ የጦርነት ማቆሚያ ጥያቄ ማቅረብ አልፈለገም። የታላቋ ብሪታንያ ሕዝብና መንግሥት በአገር ላይ የመጣውን አደጋ ለመከላከል እንደዚህ ሲተባበሩና፣ በቆረጠ መንፈስ ችግሩን ሲቋቋሙ የታየው፣ በታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ መሆኑ ይነገራል። የእንግሊዝ ንጉሥ ጆርጅ ስድስተኛ እና ንጉሣውያን ቤተሰቦቻቸው፣ በተለይ በሎንዶን ሕዝብ ላይ ጠላት ይህን ሁሉ የቦንብ መዓት ሲያወርድበት፣ እኛ ተለይተን ሕይወታችንን ለማዳን መሞከር የለብንም በማለት፣ ጦርነቱ እስከቆመበት ሰዓት ድረስ ከባኪንግሃም ቤተመንግሥታቸው አልተነቃነቁም። የካናዳና የአውስትራሊያ ኮመንዌልዝ መንግሥታት፣ የንጉሡንና የንጉሣውያን ቤተሰቦቻቸውን ሕይወት ለማዳን ወደ እኛ እንዲመጡ የጦር መርከብ እናዘጋጅ ሲሉ፣ ያቀረቡትን ጥያቄ የሚቀበላቸው አላገኙም።

እንግዲህ ! አዶልፍ ሂትለር ከጦር ሚኒስትሩ ከማሬሻል ጎሪንግ ጋር ሆኖ በፈረንሣይ ላይ እንዳደረገው፣ እንግሊዝን ለመውረር ከነሐሴ እስከ ጥቅምት 1940 ዓ.ም ድረስ፣ በምድር፣ በአየርና በባሕር ኃይሎች ያደረገው ጦርነት ምኞቱን ሊፈጽምለት አልቻለም። ይልቁንም፣ በመጨረሻ የወጣው ስታቲስቲክ እንዳመለከተው፣ የታላቋ ብሪታንያ የአየር ኃይል፣ ቁጥራቸው ከሁለት ሺህ አምስት

መቶ በላይ የሆኑትን የናዚን የጦር አውሮፕላኖች አጥቅቶ ሲያወድምበት፤ ፊዩረር መሸነፉን ለማመን ቢቸገርም፤ እንግሊዝን ለመውረር የጀመረውን ጦርነት ለጊዜው አቁሞ፤ ውጊያውን ለሌላ ምቹ ጊዜ ማስተላለፍ ግዴታ ሆነበት። በዚህ ውጤት፤ ምንም እንኳ ጦርነቱ አለቀ ማለት ባይቻልም፤ የቸርችል መንግሥት ድል አድራጊነቱ አይካድም። የሂትለር ጦር ከእንግሊዝ ደሴት ማፈግፈጉ እንደታወቀ፤ ዊንስተን በፓርለማው ሰገነት ላይ ሆኖ፤ " ... ቁጥራቸው ከጠላቶቻችን እጅግ አነስተኞች የሆኑት ንጉሣዊ የአየር ኃይል ተዋጊዎቻችን ያስገኙት ድል፤ በታላቋ ብሪታንያ ብቻ ሳይሆን በሌላውም ዓለም ታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ የሚመዘገብ ነው ... " ሲል፤ ያደረገው ንግግር እጅግ ተደናቂ ሆኖለታል።

እንደሚታወቀው፤ አንድ መሪ የሚከበረውም ሆነ የሚደነቀው፤ ጥሩ ዲስኩር በማድረጉ ብቻ ሳይሆን፤ የተናገረውንና የሰጠውን ቃል በተግባር አውሎት ሲታይ ነው። መልካም ዝና የሚገኘው፤ መልካም ዲስኩር በማድረግ ብቻ ቢሆን ኖሮ፤ የፈረንሣይ መሪዎች እነ ኤድዋርድ ዳላዲዬና እነ ፖል ሬይኖ፤ ናዚን ከምድረ ገጽ ከማውደም በስተቀር ሌላ ዓላማ የለንም ብለው ያደረጓቸው እነዚያ ሁሉ ዲስኩሮች፤ ዛሬ የታሪኩን ቦታ ሲያጣብቡት ይገኙ ነበር። ነገር ግን፤ ታሪክ ለሚከበሩትና ለሚወቀሱት ያገር መሪዎች፤ የተለያዩ ቦታዎችን አዘጋጅቶ የሚጠብቅ ስለሆነ፤ እስከ መጨረሻው ከጠላት ጋር ተዋግቶ ድልን የተጐናጸፈውንና፤ ስድስት ሳምንታት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ ደግሞ፤ ውርደትን ተቀብሎ አገሩን ለጠላት በማስረከብ የሸሸውን፤ በየመልኩ እየለየ ተገቢውን ሥፍራ ለመስጠት አይቸገርም። በዚህም መሠረት፤ የፈረንሣይ መሪዎች ስድስት ሳምንታት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፤ ከናዚ ውርደትን ሲቀበሉ ባለማፈራቸው፤ የሚወቀሱበትን የታሪክ ገጽ ማንም እንዳልያዘባቸው ሁሉ፤ ዊንስተን ቸርችልም በቆራጥነቱ እስከመጨረሻው ተዋግቶ ድል በማግኘቱ፤ ከፍተኛውን የታሪክ ክብር ለመጐናጸፍ የተዘጋጀለትን ቦታ ማንም አልነካበትም።

## ORIENTATION BIBLIOGRAPHIQUE

1. J.B. Duroselle,
   Histoire Diplomatique 1919-1970 (Dalloz)
2. Jacques Chastenet
   Vingt Ans d'Histoire Diplomatique 1919-1939
3. Le Monde Entre Deux Guerres 1919-1939
   Raymond Cartier (paris-Match)
4. Histoire De La Guerre Froide
   1917-1950 André Fontaine



" ... ዓላማህ ምንድን ነው? ብላችሁ ብትጠይቁኝ፤ በምድር በአየርና በባሕር ከጠላታችን ጋር መዋጋት ነው እላችኋለሁ። ግብህስ ምንድን ነው? ብትሉኝ፤ ጠላትን አሸንፈን ድልን መጎናጸፍ መሆኑን እገልጽላችኋለሁ ... "
(ዊንስተን ቸርችል ግንቦት 1940 ዓ.ም)

# ክፍል ፭

# የተበደለች ኢትዮጵያ

## ፀሎቷ ተሰማ

### ፋሽስትን ከኢትዮጵያ ለማባረር የእንግሊዞች ውሳኔና እርምጃ

# ምዕራፍ ፩

## እንግሊዞች ፊታቸውን ወደ ኢትዮጵያ !

እ.ኤ.አ ሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም (እንደ ኢት.አቆ ሰኔ 23/1928) የጄኔቮ የመንግሥታት ማኅበር፤ የፋሽስት መንግሥት የኢትዮጵያን ነፃነት ለመደምሰስ ባደረገው ሕገ ወጥ ጦርነት በዓለም ላይ የተወሰነበት የኢኮኖሚ እገዳ ቅጣት እንዲሰረዝለት፤ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት መልዕክተኛ የቀረበውን ሐሳብ አስተባብሮ፤ በታሪክ ላይ ምንጊዜም የማይረሳውን አሳፋሪ የሆነ የግፍ ፍርድ መስጠቱ ይታወሳል።

የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና መንግሥታቸው፤ ምንም እንኳ ከእንግሊዞች ያልጠበቁትና ያላሰቡት አሳዛኝ በደል ቢደርስባቸውም፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ዛሬ ለጥቅሙ ሲል ያደረገውን ስህተት ነገ ተጸጽቶ ኢትዮጵያን ይክሳት ይሆናል የሚል ተስፋ በማሳደር፤ ቅሬታቸውንም ሆነ ጥልቅ ሐዘናቸውን ማሳወቅ አልፈለጉም። ታላቋ ብሪታንያም በሙሶሊኒ መንግሥት ላይ ተወስኖ የነበረው የኢኮኖሚ እገዳ ቅጣት፤ እስከዛሬ እንደታየው አንዳች ውጤት ስላልሰጠ፤ መቆየቱ አይጠቅምም በማለት ቅጣቱ እንዲሠረዝ ጥያቄ ብታቀርብም፤ ሊግ ኦፍ ኔሽንና አባል መንግሥታት በሙሉ፤ ኢትዮጵያ በፋሽስት መያዟን ዕውቅና እንዳይሰጡ የጠነከረ ማሳሰቢያ መስጠቷን፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አንድ ዓይነት እርዳታ ነው ብለው ተቀብለውታል። በተጨማሪም፤ ለኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት የስደት ማረፊያ ለመስጠት፤ የፈረንሣይና የስዊስ መንግሥታት በሩን ሲዘጉባቸው፤ የሚችለውን አድርጐ የተቀበላቸው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በመሆኑ፤ በውለታ አስበውታል።

እ.ኤ.አ ከ1937 ዓ.ም እስከ 1940 ዓ.ም ድረስ፤ የታላቋ ብሪታንያ ጠቅላይ ሚኒስትር የነበረው የኮንሴርቫተር ፓርቲ ኔቪል ቻምበርሌን (Neville Chamberlain) የሁለተኛውን የዓለም ጦርነት ለማዳን ጠንቀኞች የሆኑትን ሂትለርንና ሙሶሊኒን በወዳጅነት እያቀረበ የሚፈልጉትን መፈጸም ይበጃል ብሎ የሚያምን ነበር። በዚህ መሠረት፤ የኢትዮጵያ ነፃነት ከተያዘ ከሁለት ዓመት በኋላ እ.ኤ.አ በየካቲት 1938 ዓ.ም ኔቪል ቻምበርሌን ከቤኒቶ ሙሶሊኒ ጋር ለመቀራረብ ፍላጐቱን ሲገልጽለት ዲክታተሩ የሚከተለውን ግዴታ እንዲፈጽም አቀረበለት። " ... የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት፤ ጣልያን በኢትዮጵያ ላይ ያለውን ይዞታ በይፋ ካወቀለት፤ የፋሽስቱ መንግሥት ኔቪል ቻምበርሌን የሚፈልገውን፤

1ኛ/ በኢስፓኝ በተነሣው የእርስ በርስ ጦርነት፤ ጣልያን ለዲክታተሩ ለጄኔራል ፍራንኮ የሚሰጠውን የጦር እርዳታ ለማቆም፤

2ኛ/ ከናዚስቱ መሪ ከአዶልፍ ሂትለር ጋር ከዲፕሎማቲክ ግንኙነቶች በስተቀር፤ ለመላው ዓለም በተለይም ለአውሮፓ አገሮች ሰላም ጠንቅ የሚሆን ምንም

ዓይነት ስምምነት ማድረግ እንደማይፈልግ፣ ቃል ለመስጠት ዝግጁ መሆኑን አስታወቀ።

ጠቅላይ ሚኒስትር ቻምበርሌን አርቆ ባለማሰብ ይሁን ወይም በየዋህነት፣ የሙሶሊኒን ሐሳብ ተቀብሎ ለስምምነቱ ዝግጅት መልዕክተኞቹን ወደ ሮም ሲልክ፣ በካቢኔው ውስጥ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትር የሆነው አንቶኒ ኢደን (Anthony Eden) አልስማማም ብሎ የሥራ መልቀቂያ ደብዳቤውን አቀረበለት።

ኢደን ይህንን እርምጃ ሲወስድ በሰጠው አስተያየት፣

1ኛ/ ከሁለት ዓመታት በፊት (በ30/06/1936) በሊግ ኦፍ ኔሽን ሸንጎ ላይ ታላቋ ብሪታንያ በሰጠችው መግለጫ፣ የፋሽስት መንግሥት በጦር ኃይል ኢትዮጵያን በመያዙ ከሊግ ኦፍ ኔሽን አባሎች ዕውቅና እንዳይሰጠው በጥብቅ ያሳሰበች መሆኗ መዘንጋት የለበትም።

2ኛ/ ከዩናይትድ ስቴትስ መንግሥት ከፕሬዚዳንት ሩዝቬልት ጋር ታላቋ ብሪታንያ ባደረገችው ንግግር፣ በኢትዮጵያ ነፃነት ላይ ያንሠራራውን የሙሶሊኒን መንግሥት ማወቅ የሰብንም ተብሎ የተደረገውን ስምምነት ማፍረስ ተገቢ አይደለም።

3ኛ/ የፋሽስት መንግሥት በግፍ ተነሥቶ የአንድን አገር መንግሥት ነፃነት ገፍፎ ቅኝ ግዛቴ አድርጌዋለሁ ብሎ ሲያውጅ፣ የታላቋ ብሪታኒያ መንግሥት ዕውቅና ከሰጠ፣ በዓለም ታሪክ ላይ ክብሩን የሚያዋርድና የሚያስወቅሰው እንደሚሆን መታሰብ አለበት።

4ኛ/ ከፋሽስቱ መሪ ከሙሶሊኒ ጋር የሚደረግ ስምምነት ሁሉ፣ የሚከበርና ዕምነት የሚጣልበት አለመሆኑን መገንዘብ ያስፈልጋል።

አንቶኒ ኢደን በእነዚህ በደረደራቸው ምክንያቶች ላይ ተመርኩዞ፣ የውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነቱን ሥልጣን ሲለቅ፣ የገለጻቸውን አስተያየቶችና በተለይም ከሙሶሊኒ ጋር የሚደረግ ውል አይጸናም ሲል የሰጠውን ማስጠንቀቂያ ማንም አላዳመጠውም። ጠቅላይ ሚኒስትር ቻምበርሌን ከሙሶሊኒ ጋር ተደራድሮ፣ ኢትዮጵያ ነፃነቷ ተደምስሶ በፋሽስቱ መንግሥት የምትተዳደር መሆኗን የሚያረጋግጥ ዕውቅና ሰጠ።

ዱቼ ሙሶሊኒ የሚፈልገውን ካገኘ በኋላ፣ ኢደን እንደታየው በተለመደው አታላይ ጠባዩ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ጋር ያደረገውን ስምምነት በመጣስ፣ ፩ኛ/ በኢስፓኝ ሥልጣን ለመያዝ ለሚዋጋው ለጄኔራል ፍራንሲስኮ ፍራንኮ በብዙ ሺህ የሚቆጠሩ ወታደሮችና የጦር መሣሪያዎች ላከ። ቀጥሎም ከሂትለር ጋር በወዳጅነት ተሰጥፎ፣ ናዚስቱ መሪ ግዛቱን ለማስፋፋት በአውሮፓ አገሮች ላይ ለሚያዘጋጀው ሤራ፣ የተባባሪነትና የአማካሪነት ሥራውን ቀጠለ።

ጠቅላይ ሚኒስትር ቻምበርሌን በኢትዮጵያ ላይ በወሰደው እርምጃ፣ ያልታዘበው የለም። በተለይም የዩናይትድ ስቴትስ ኦፍ አሜሪካ፣ የሶቪየት ሕብረት ሬፑብሊክና የቻይና መንግሥታት ከፍ ያለ ቅሬታቸውን ከማሰማት አልተቆጠቡም። ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴም ከፍ ያለ ዕምነት የተጣለበት የታላቋ ብሪታንያ

መንግሥት በኢትዮጵያ ላይ በፈጸመው በደል፣ ጊዜው ሲደርስ አንድ ቀን ብድሩን እንደሚከፍል ለፈጣሪያቸው ከማመልከት በስተቀር፣ በአደባባይ ወጥተው ሐዘናቸውን ለመግለጽ ያሉበት ሁኔታ አልተመቻቸውም።

ኔቪል ቻምበርሌን ከሙሶሊኒ ያገኘው ኤክስፔሪያንስ ትምህርት አልሆነውም። በኢትዮጵያ ላይ የፋሽስትን ይዞታ ዕውቅና በሰጠ ስድስት ወራት ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ በመስከረም 29 ቀን 1938 ዓ.ም በሙኒክ (Munich) ጉባኤ ላይ ደግሞ፣ ከፈረንሣይ መንግሥት መሪ ከኤድዋርድ ዳላዲዬ (Edouard Daladier) ጋር ሆነው የቼኮስሎቫኪያን ነፃነት ለናዚስቱ መሪ እንደገጸ በረከት በማቅረብ፣ የአውሮፓ ሕዝቦች ከጦርነት ዕልቂት ዳኑ ብለው፣ በየአገራቸው ትርጉም የሌለው ትልቅ የደስታ ጩኸት ሲያሰሙ ሰነበቱ። ይሁን እንጂ፣ ሂትለር ይህንን ስጦታ በቂ ነው ብሎ አልተቀበለውም። ለአንድ ዓመት ያህል ሰላም ፈላጊ መስሎ እያታለላቸው የጦር ድርጅቱን ሲያከማች ከኖረ በኋላ፣ መስከረም 1 ቀን 1939 ዓ.ም ባልተጠበቀ ሰዓት በድንገት ተነሥቶ ፖላንድን ወረረ። ከአንድ ዓመት በፊት በሙኒክ ጉባኤ ላይ ጦርነትን አስወገድን ብለው በሚያስገርም ሁኔታ በደስታ ሲጨፍሩ የነበሩት የእንግሊዝና የፈረንሣይ መሪዎች፣ የሚቀጥለው የአዶልፍ ሂትለር እርምጃ በእነሱ ላይ የተጠመደ መሆኑን ዘግይተው ተረዱት። ስለዚህም፣ ፖላንድ ከተወረረች ከሁለት ቀናት በኋላ፣ መስከረም 3 ቀን 1939 ዓ.ም እንግሊዝና ፈረንሣይ በናዚ መንግሥት ላይ ጦራቸውን መዘዘው፣ የሁለተኛውን የዓለም ጦርነት መክፈት ግዴታቸው ሆነ።

ቤኒቶ ሙሶሊኒም፣ በዚያው ቅጥፈት በተመላበት ፖለቲካው በአንድ በኩል እኔ በዚህ ጦርነት ውስጥ ተካፋይ አይደለሁም እያለ፣ እንግሊዞችንና ፈረንሣዮችን ሲያታልል፣ በሌላ በኩል ደግሞ አዶልፍ ሂትለር ከጐኑ ተሰልፎ እንዲዋጋ እስከሚጠይቀው ድረስ፣ የጦር ትጥቁን በማዘጋጀት ዘጠኝ ወራት ከቆየ በኋላ፣ ሰኔ 10 ቀን 1940 ዓ.ም በታላቋ ብሪታኒያና በፈረንሣይ መንግሥታት ላይ ጦርነቱን አወጀ።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ እ.ኤ.አ በሰኔ 30 ቀን 1936 ዓ.ም በገኔቭ የመንግሥታት ማህበር ሸንጐ ላይ " የፍርድ ያለህ! " በሚለው ትንቢታዊ ንግግራቸው፣ የፋሽስት መንግሥት ዛሬ በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ የሚፈጽመውን ግፍ፣ ነገ በሌሎች አገሮች ላይ ለማድረግ ምን ያግደዋል? ተብሎ በዓለም ላይ ለቀረበው ትልቅ ጥያቄ መልስ ያልተሰጠ መሆኑን ካስታወሱ በኋላ፣ " ... ፋሽስት በግፍ ተነሥቶ የሚጥለው አደጋ፣ በድሆች አገሮች ላይ ብቻ ተወስና እንደማይቀር የታወቀ ስለሆነ፣ ታላላቆችም መንግሥታት ነገ እንደሚደርስባችሁ ብታስቡበት ይሻላል ... " ሲሉ የሰጡትን ማሳሰቢያ፣ በዚያን ዘመንና በዚያን ሰዓት ያዳመጣቸው ወይም የተረዳላቸው አልነበረም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ይህንን ታሪካዊና ልባዊ የሆነ ስሜት ለዓለም ሕዝብ በገለጹ ልክ በአራተኛው ዓመት፣ በሰኔ 1940 ዓ.ም ዱቼ ሙሶሊኒ ከፉሬር ሂትለር ጋር ተሰልፎ እንግሊዝንና ፈረንሣይን ለመውጋት ጦርነት መክፈቱን አስታወቀ።

እንግዲህ ! እንግሊዝና ፈረንሣይ ምን ማድረግ ይኖርባቸዋል? .... ሳይወዱ በግድ ከናዚና ከፋሽስት ዲክታተሮች የመጣባቸውን አደጋ በጦር ሜዳ ከመዋጋትና አሸንፈው በዓለም ላይ ያላቸውን ክብር ከመጠበቅ በስተቀር ሌላ መንገድ አልነበራቸውም። በተለይ እንግሊዞች፣ ከዲክታተሮቹ ከሂትለርና ከሙሶሊኒ ጋር

ተግባብቶ በሰላም መኖር ይቻላል ብሎ በደካማነት መንፈስ ሲያጉነብስ በቆየውና የጦር ዝግጅቱን ጊዜ በከንቱ ባቃጠለው በቀድሞው ጠቅላይ ሚኒስትር በኔቪል ቻምበርሌን ላይ ያሳደሩት ቅሬታ በቀላሉ የሚገመት አልሆነም። ለዚህ መድኃኒቱ አዲስና ጠንካራ መንግሥት ማቋቋም ስለሆነ፣ የመላውን ሕዝብና በአገር ውስጥ ያሉትን የፖለቲካ ድርጅቶች ትብብር ማግኘት እጅግ አስፈላጊ ነበር። በዚህም መሠረት በታሪክ ለመጀመሪያ ጊዜ የኮንሴርቫተር፣ የሌበርና የሊበራል ፓርቲዎች በአንድነት ተስማምተው የጋራ የሆነ የጦር ካቢኔ (መንግሥት) አቋቋሙ። ይህንንም አዲስ መንግሥት በጠቅላይ ሚኒስትርነት እንዲመራ ከኮንሴርቫተሮች ፓርቲ የተመረጠው ዊንስተን ቸርችል (Winston Churchill) ሲሆን፣ የጦር ሚኒስትሩ ደግሞ ከሁለት ዓመታት በፊት በኢትዮጵያ ጉዳይ ከቻምበርሌን ጋር አልስማማም ብሎ ከውጭ ጉዳይ ሚኒስትርነቱ ለቅቆ የወጣው አንቶኒ ኤደን ሆነ። እንደሚታወቀው ኤደንም የኮንሴርቫተር ፓርቲ አባል ነው።

ይህ አዲስ መንግሥት ተቋቁሞ ሥራውን በጀመረ ወር ባልሞላ ጊዜ ውስጥ፣ ጠቅላይ ሚኒስትሩ ቸርችልና የጦር ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን ተነጋግረው፣ በኢትዮጵያ ላይ የተደላደለውን የሙሶሊኒን አስተዳደር ለማባረር አስፈላጊነቱን ቅድሚያ ሰጡት። በዚህ መሠረት፣ ስደተኛ ሆነው በሎንደን የሚገኙት ንጉሠ ነገሥት ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በአስቸኳይ ወደ ሱዳን ተጉዘው፣ በኢትዮጵያ ያሉትን የነፃነት ተዋጊ አርበኞች አስተባብረው እየመሩ፣ ከታላቋ ብሪታንያ በሚሰጣቸው የጦር እርዳታ የአገራቸውን ነፃነት እንዲያስመልሱ ያቀረቡትን ጥያቄ ደገፏቸው።* ይህችን አለአግባብ በግፈኛው ፋሽስት ጦር ተይዛ ነፃነቷ የተገፈፈውን ኢትዮጵያን ነፃነቷን ለማስመለስ ቸርችልና ኤደን የተስማሙበትን፣ ኮንሴርቫተሮች ብቻ ሳይሆኑ ሌሎቹም የሌበርና የሊበራል ፓርቲዎች አባሎች በሙሉ የሚደግፉት ሆነ። ከዚህም በላይ በኢትዮጵያ ላይ በደረሰው የፋሽስት ግፍ እጅግ ሲያዝን የቆየውም የእንግሊዝ ሕዝብ፣ አዲሱ ካቢኔ ይህችን የተበደለች አገር የነፃነት መብቷን ለማስከበር ያደረገውን ውሳኔ በደስታ ተቀበለው።

የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ውሳኔ እንደተገለጸ፣ በኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥትና በኢትዮጵያ ሕዝብ ዘንድ ያገኘው ተቀባይነትና የሰጠው ደስታ፣ መጠኑ ምን ያህል እንደሆነ መገመት የሚቻል አልነበረም። ወዲያውም አዲሱ ጠቅላይ ሚኒስትር ዊንስተን ቸርችልና ካቢኔው፣ ከዚህ በፊት የኔቪል ቻምበርሌን መንግሥት፣ በኢትዮጵያ ላይ የሙሶሊኒን ይዞታ የሰጠው ዕውቅና ፍጹም የተሻረ መሆኑን፣ ለእንግሊዝ ሕዝብና ለመላው ዓለም ካስታወቀ በኋላ፣ ንጉሠ ነገሥት ኃይለሥላሴ ወደ ሱዳን የሚጓዙበትን ትራንስፖርት አዘጋጅቶ ሰጠ። እንግዲህ ! ይህች የተበደለችና ብዙ ግፍ የተቀበለች ኢትዮጵያ በአምላክ ቸርነት የጸሎቷ መሰማት መታየት ጀመረ ማለት ነው።

* FO-371 27516

# ምዕራፍ ፪

## ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በሱዳን

እ.ኤ.አ ሰኔ 10 ቀን 1940 ዓ.ም ሙሶሊኒ ከሂትለር ጋር መሰለፉን አስታውቆ፣ በታላቋ ብሪታንያ እና በፈረንሣይ መንግሥታት ላይ ጦርነት ባወጀ በሁለተኛው ሳምንት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከሎንዶን ተነሥተው በባሕር ላይ እየተነሳፈፈ በሚበር አውሮፕላን ወደ ሱዳን ሄዱ።

ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ካርቱም የተጓዙት፣ በኢትዮጵያና በሱዳን አካባቢ የሚኖሩትን ተዋጊ አርበኞች በማሰባሰብና ከታላቋ ብሪታንያ በሚያገኙት የጦር እርዳታ፣ በፋሽስት ላይ ለመዝመት ያቀረቡትን ጥያቄ የዊንስተን ቸርችል ካቢኔ ስለተቀበለው ነበር። በዚህ መሠረት፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ልጃቸውን ልዑል መኰንን ምስፍን ሐረርን፣ ረዳቶቻቸውን አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስንና አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝን ብቻ አስከትለው፣ እ.ኤ.አ ሰኔ 24 ቀን 1940 ዓ.ም ከሎንዶን ተነሥተው ማልታ ደሴት ላይ አዳር አደረጉ። ከዚያም በማግሥቱ ግብፅ አገር ደርሰው ወደ ካርቱም ለመሄድ በአውሮፕላን ሲሳፈሩ፣ የሱዳን ጠቅላይ ገዥ ሰር ስትዋርት ሳይምስ፣ የሱዳን ጦር ጠቅላይ አዛዥ ዤኔራል ዊሊያም ፕላት (Sir Stewart Symes and General Platt) ያልታሰበ ችግር ፈጠሩባቸው። ስለ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ወደ ሱዳን መምጣትና ግቡም ለምን እንደሆነ የምናውቀው ነገር ስለሌለ፣ ከካይሮ የተሳፈሩበት አውሮፕላን ካርቱም በመውረድ ፋንታ፣ ወደ ሌላው የሱዳን ግዛት ዋዲ ሐልፋ* ወደተባለው በረሃማ ቦታ ሄዶ እንዲያርፍ በማለት ትዕዛዝ ሰጡ።

አገረ ገዥውና የጦሩ አዛዥ፣ ንጉሠ ነገሥቱን በመጠኑም ቢሆን ተገቢነት ያለው ማረፊያ በሌለበት እጅግ በረሃማ በሆነ ቦታ ወስደው ሲዘጉባቸው፣ የሰጧቸው ምክንያቶች የሚከተሉት ነበሩ።

1ኛ/ ቀደም ሲል ባጭሩ እንደተገለጸው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ካርቱም መምጣታቸውንና እዚህ ቆይተው የሚፈጽሙትን፣ የጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ጽሕፈት ቤት ሆነ ወይም ደግሞ የጦር ሚኒስትሩ የአንቶኒ ኤደን ቢሮ የሰጠው መምሪያ ባለመኖሩ፣

2ኛ/ በኢትዮጵያ ግዛት ላይ የሠፈረው የፋሽስት ጦር ኃይል ከሙሉ የመሣሪያ ትጥቅ ጋር ዘጠኝ መቶ ሺህ ወታደሮችና ሁለት መቶ የቦንብ ጣይ አውሮፕላኖች ያሉት ሲሆን፣ ንጉሠ ነገሥቱ እንደፈለጉት በምን አኳኋን ነው? .... ይህንን የሚመክት ጦር ካርቱም ላይ ማዘጋጀት የሚቻለው? ....

* (Ouadi - Halfa)

በግንቦት 1940 ዓ.ም የተቋቋመው የዊንስተን ቸርችል የጦር ካቢኔ አባሎች፤



በመጀመሪያው ረድፍ ከግራ ወደ ቀኝ ሁለተኛውን ወንበር የያዘው ቸርችል ሲሆን፤ በአራተኛው ወንበር ላይ ያለው የጦር ሚኒስትሩ አንቶኒ ኤደን ነው፤

3ኛ/ የንጉሡ ነገሥቱን ካርቱም መገኘት የጠላት መረጃ ካወቀው፤ የሚያደርስብን አደጋ ከፍ ያለ ስለሆነ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ለጥበቃ እንዲያመች ወደ ዋዲ ሐልፋ ወስደናቸዋል የሚል ነው።

ይሁን እንጂ እነዚህን የተሰጡትን ምክንያቶች ላይ ላዩን ለሚያዩት አንዳንድ እውነት የሆኑ ነጥቦች የሚታዩበት መስለው ቢገመቱም፤ በጥልቀት ለሚመለከቱት ደግሞ፤ የሰር ስትዋርት ሳይምስ እና የገኔኔራል ዊሊያም ፕላት መሠረታዊ አቋም ፍጹም የሆነ የኮሎኒያሊስት አሠራር መሆኑን ለመገንዘብ አያስቸግርም። የእነዚህ ሰዎች መሠረታዊ ዕምነት፤ ፋሽስትን ከኢትዮጵያ ግዛት ለማባረር የሚደረጉት ውጊያዎች፤ ከድል በኋላ አገሪቱን በታላቋ ብሪታንያ መንግሥት አስተዳደር ውስጥ ለማስገባት ነው እንጂ፤ ኢትዮጵያ ነፃነቷን አግኝታ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ዘውድ ለመመለስ አይደለም። ስለዚህም፤ ታላቋ ብሪታንያ በፋሽስት ላይ ለምታደርገው ዘመቻ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ምንም ዓይነት ጥቅም ስለማይሰጡ ወደመጡበት ወደ ሎንዶን ቢመለሱ ይሻላል የሚል ሐሳብ ነበራቸው።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ደግሞ በበኩላቸው፤ በዚያ የፀሐይ አሩርና ሙቀት በሰፈነበት በዋዲ ሐልፋ በረሃ ብዙ ሥቃይ እየተቀበሉ፤ የኢትዮጵያን ነፃነት ለማስመለስና የወደፊቷን ኢትዮጵያን ለመገንባት የነደፏቸው ፕላኖች የሚከተሉት ነበሩ።

1ኛ/ በኢትዮጵያ ውስጥና በአካባቢው አገሮች የሚገኙትን አርበኞች ከአሰባሰቡ በኋላ፤ በሱዳን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የሚያስፈልጋቸውን የአየር ኃይልና የምድር ጦር አዘጋጅቶላቸው፤ በእሳቸው መሪነት የፋሽስትን ጦር ለመደምሰስና የኢትዮጵያን ነፃነት ለመመለስ እንዲያስችላቸው፣

2ኛ/ ፋሽስት ድል ሆና ከመላ ኢትዮጵያ ሲባረር፤ ጥንት የኢትዮጵያ ግዛቶች የነበሩት ኤርትራና ሱማሌ ከእናት አገራቸው ከኢትዮጵያ ጋር እንዲቀላቀሉ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ሙሉ እርዳታ እንዲሰጣቸው፣

3ኛ/ ከጂቡቲ እስከ አዲስ አበባ የተዘረጋው የኢትዮጵያና የፈረንሣይ የምድር ባቡር፤ አሁን ከተያዘበት ከፋሽስት እጅ ሲላቀቅ፤ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት መንግሥት እንዲረከበው የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ድጋፋን እንዲሰጣቸው፣

4ኛ/ ፋሽስት ኢትዮጵያን ለቅቆ ከወጣ በኋላ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አዲሱ መንግሥታቸውን በዘመናዊ ሥርዓት ሲያቋቁሙ፤ አገሪቱን ለማስተዳደሪያ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት አስፈላጊውን የሥራ ማስኬጃ በጀት ለተወሰነ ጊዜ እንዲያበድራቸው፣

5ኛ/ የቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አዲሱ መንግሥት እንደተቋቋመ፤ ለየሥራው ዘርፍ የሚያስፈልጉትን አማካሪዎችና ባለሞያዎች፤ በኢትዮጵያ በጀት የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እንዲመድብላቸው፣ የንጉሠ ነገሥቱ ብርቱ ምኞትና ፍላጐት ነበር።

እዚህ ላይ እንደሚታየው፣ የጃንሆይና በሱዳን ያሉት የእንግሊዝ የጦር ባለሥልጣኖች ሐሳብ ጨርሶ የተለያየ ነው። ቸርችልና ኢደን ደግሞ የናዚ እና የፋሽስት ኃይል ተደማምሮ ስለመጣባቸውና ፈረንሣይም ድል ሆና በቶሎ በመውደቋ ብቻቸውን ስለሆኑ፣ በዚያ አስቸጋሪ ሰዓት የኢትዮጵያን ጉዳይ ለመከታተል የሚያስችል ጊዜ አልነበራቸውም። ለእነዚህም ለዕብሪተኞቹ ለእነ ጄኔራል ፕላት የተመቻቸው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ከሎንዶን ተሳፍረው ወደ ሱዳን ሲመጡ፣ ከጠቅላይ ሚኒስትሩም ሆነ ወይም ከጦር ሚኒስትሩ ምንም ዓይነት መምሪያ ያልተላከላቸው መሆኑን ሰበብ በማድረግ ነው። እነዚህ ሰዎች ቅንነትና መልካም መንፈስ ያላቸው ቢሆኑ ኖሮ፣ በተለይ የሱዳን ጠቅላይ ገዥ ሰር ስትዋርት ሳይምስ ወደ ሎንዶን መልዕክት ልከው፣ ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ካርቱም የመጡበትን ጉዳይና ሊደረግላቸው የሚገባውን እርዳታ መጠየቅ ይችሉ ነበር። ነገር ግን በሱዳን ያሉት እነዚህ ባለሥልጣኖች ይህንን የመሰለ እርምጃ ለመውሰድ አልሞከሩም።

የእነሱ ዋና ፍላጎት፣

1ኛ/ ልጃቸውንና ሁለት ረዳቶቻቸውን ብቻ ይዘው የመጡት ንጉሠ ነገሥት፣ በሱዳን ምንም ማድረግ የማይችሉ መሆናቸውን ተገንዝበው፣ በብስጭት ወደ ስደት ቤታቸው ወደ ሎንዶን እንዲመለሱ ለማስደረግ፣

2ኛ/ንጉሠ ነገሥቱ ወደ ሎንዶን እንደተመለሱ፣ አስፈላጊውን የጦር ዝግጅት አሟልተው ወደ ኢትዮጵያ ግዛት በመዝለቅ የፋሽስትን ኃይል ደምስሶ ለማባረርና፣ በፋሽስት ቦታ በኢትዮጵያ ላይ የታላቋ ብሪታንያን አስተዳደር ለመመሥረት ነው።

በእነዚህ ሐሳቦች ቸርችልና ኢደን እንደማይስማሙ የታወቀ ቢሆንም፣ የሱዳን ገዥና የጦሩ አዛዥ በዚህ በሚከተሉት ዕምነት፣ ንጉሠ ነገሥቱን በማበሳጨትና ሞራላቸውን በማዳከም ላይ መሆናቸውን እውነተኛውን ሁኔታ ገልጸ የነገራቸው የለም። ጃንሆይ ከካይሮ ሲነሡ፣ ለአንዳንድ ጉዳይ በምክር እንዲረዳቸው የተመደበላቸው እንግሊዛዊው ዲፕሎማት ቻፕማን አንድሪውስ (Chapman-Andrews) ከዋዲ ሐልፋ ተነሥቶ ካርቱም በመምጣት ንጉሠ ነገሥቱ ሱዳን ከመጡበት ቀን ጀምሮ የደረሰባቸውን ችግር ዘርዝሮ ለጄኔራል ዊሊያም ፕላት አመለከተ። ፕላት መጀመሪያ እንደተናገረው፣ ፋሽስትን ከኢትዮጵያ ግዛት ለማባረር ለሚደረገው የጦር ዝግጅት፣ ንጉሠ ነገሥቱ ያስፈልጉናል ብዬ አላምንም። በዋዲ ሐልፋ የአየሩ ጠባይ ካስቸገራቸውና ሕይወትን መቋቋም ካልቻሉ፣ ወደመጡበት ወደ ሎንዶን እንዲመለሱ ትራንስፖርቱን እናዘጋጅላቸዋለን የሚል መልስ ሰጠ። ቻፕማን አንድርውስ በጄኔራሉ አነጋገር በጣም አዝኖ፣ ይህ ሐሳባችሁ በኃላፊነት የሚያስጠይቃችሁ እንደሚሆን እርግጠኛ ነኝ የሚል የዛቻ ቃል ተናግሮ ወደ ዋዲ ሐልፋ ተመለሰ። ወዲያም ጃንሆይ የሱዳን ጦር አዛዥና አገረ ገዥ የሚፈጽሙባቸውን በደል በመዘርዘር፣ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል እንዲያመለክቱ የቴሌግራሙን ረቂቅ አዘጋጅቶ አቀረበላቸው። ጃንሆይ ይህንን ከአማካሪያቸው የቀረበላቸውን ሐሳብ መቀበል አልፈለጉም። የጃንሆይ አስተያየት፣ " ... እኔ ከሎንዶን ወደ ሱዳን የመጣሁበትን ጉዳይ ሚስተር ቸርችልና ሚስተር ኢደን ደህና አድርገው ያውቃሉ። እዚህ ከደረስኩ በኋላ በምን ሁኔታ ላይ እንደምገኝና የመጣሁበትንም ጉዳይ ለማዘጋጀት ምን ያህል እርምጃ እንደተደረገ፣ በሱዳን ያሉትን ባለሥልጣኖቻቸውን ጠይቀው መረዳት፣ የጉደለውንም በአስቸኳይ

እንዲያሟሉ መምሪያውን መስጠት፤ የጠቅላይ ሚኒስትሩና የጦር ሚኒስትሩ ተግባር ነው። ስለዚህም፤ እኔ ይኸ ጉዳይ ! ይኸ ቀረ ! እያልኩ አመልካች መሆን የለብኝም ....” የሚል ሆነ።

ቻፕማን አንድርውስ በጣም ተገረመ። እኝህ ንጉሥ ብርታታቸውንና ትዕግሥታቸውን ሳደንቅ፤ በሌላ በኩል ደግሞ ክብራቸውን ለመጠበቅ ሲሉ መጉዳትን መምረጣቸው ያሳዝነኛል። እንግዲህ በእኔ ላይ የሚደርሰውን ሁሉ እቀበላለሁ። ንጉሠ ነገሥቱን በባቡር ወደ ካርቱም ልውሰዳቸውና በዚያ አገረገዥውና የጦር አዛዡ ተቀብለው እንዲያነጋግሯቸው ማድረግ አለብኝ ብሉ ተነሣ። በዚህ ሐሳብ ጃንሆይም ተስማሙ። ቻፕማን አንድርውስ እነ ዤኔራል ፕላትን እስከዚህ ለመድፈር የሞከረው፤ አንድ ዓይነት የማስፈራሪያ መንገድ ይዞ ነው። ይኸውም፤ እኔ ለቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ልዩ ረዳትና አማካሪ ሆኜ እንድሠራ የተመደብኩት በቀጥታ ከጦር ሚኒስትሩ ከአንቶኒ ኢደን ስለሆነ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ጉዳይ ለመፈጸም ኃላፊነት አለብኝ የሚለው አቋሙ ነው። ቻፕማን አንድርውስ፤ በሰኔ ወር መጨረሻ ላይ ንጉሠ ነገሥቱ ከዋዲ ሐልፋ በባቡር ተጉዘው ካርቱም ሲገቡ፤ ማረፊያ እንዲዘጋጅላቸውና ተቀባይም እንዲደረግላቸው ለፕላት ቢሮ አስታውቆ ስለነበረ፤ ጃንሆይ እንደደረሱ፤ በአውቶሞቢል ከከተማው ሠላሳ ማይልስ ያህል ርቆ አባይ ወንዝ አጠገብ በሚገኘው ጀበል አውልያ በተባለው ቦታ ሔደው እንዲያርፉ ተደረገ። ይህም የተመረጠው የማረፊያ ቦታ፤ ለንጉሠ ነገሥቱ ፀጥታ መጠበቂያ ይመቻል ተብሎ ሲሆን፤ ጃንሆይም ዋዲ ሐልፋ ከነበሩበት የተሻለ ሆኖ ስለአገኙት ደስ ብሏቸዋል። ሆኖም፤ የጀበል አውልያ መኖሪያ ከዋዲ ሐልፋ ጋር ሲመዘን የተሻለ ነው ቢባልም፤ ንጉሠ ነገሥቱ እንደፈለጉ ለመንቀሳቀስና በአገር ውስጥም ሆነ በውጭ አገር ከሚገኙት ከኢትዮጵያውያን አርበኞችና ስደተኞች ጋር እየተገናኙ ዘመቻውን ለማዘጋጀት፤ የነዤኔራል ፕላትን ስምምነት አላገኙም። ለዚህም ሁኔታ ባለሥልጣኖቹ የሚሰጡት ምክንያት፤ በኢትዮጵያ የሠፈረው የፋሽስት ጦር ኃይል በጣም ከፍተኛ ስለሆነ፤ የንጉሠ ነገሥቱን ደህንነት በጥንቃቄ መጠበቅ ያስፈልጋል የሚል ነው።

ጃንሆይ ከዋዲ ሐልፋ ወደ ካርቱም የመጡበት ትልቁ ምክንያት፤ የሱዳንን ጠቅላይ ገዥ ሰር ስትዋርት ሳይምስንና የጦሩን ዋና አዛዥ ዤኔራል ዊሊያም ፕላትን በቀይታ ለማነጋገር ስለሆነ፤ እነሱን በቀጠሮ ለማግኘት ያስፈለገው ጥረት ቀላል አልነበረም። በመጀመሪያ ያነጋገሩት ዤኔራል ፕላትን ሲሆን፤ እሱም ከዚህ በፊት ስለ ጃንሆይ ወደ ሱዳን መምጣት ካሳየው ተቃውሞና የእብሪት መንፈስ፤ በመጠኑ የተሻሻለ ሁኔታ ቢታይበትም፤ ንጉሠ ነገሥቱ ላቀረቡለት የእርዳታ ጥያቄ ምንም ዓይነት የተጨበጠና ለወደፊቱም ተስፋ ይሆናል የሚባል ነገር ሊገልጽላቸው አልፈለገም። እየደጋገመ የነገራቸው፤ ጃንሆይ ከሉንዶን ወደ ሱዳን የመጡት ያለ አንዳች ዝግጅት ስለሆነ፤ እሳቸው እንደሚፈልጉት ጦር አዘጋጅተው በፋሽስት ላይ ለመዝመት ጊዜ የሚወስድና ከፍተኛ ትዕግሥት የሚጠይቅ መሆኑን ነው።

ከዤኔራል ፕላት በኋላ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ተቀብሉ ያነጋገራቸው አገረ ገዥው ሰር ስትዋርት ሳይምስም፤ ለንጉሠ ነገሥቱ ክብር ከፕላት የተሻለ አስተያየትና አቀራረብ ያለው ቢሆንም፤ በመሠረታዊው አቋሙ ከፕላት የተለየ ሐሳብ አልነበረውም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴም በሰፊው ለማስረዳት የሞከሩት፤ ከሉንዶን ተነሥተው ሱዳን ከገቡበት ጊዜ ጀምሮ፤ አንዳች ቁም ነገር ያለው ሥራ ለመጀመር ባለመቻላቸው እጅግ ማዘናቸውን ነበር። አገረ ገዥው ደግሞ በበኩሉ

ሰር ስቲዋርት ሳይምስ፤ የታላቋ ብሪታንያ የሱዳን ገዥ



ጃንሆይ ሱዳን ሲደርሱ፤ በአቀባበልም ሆነ ማረፊያ በመስጠት በድሏቸዋል፤

በትክክል የሚያስበውን በግልጽ ከመናገር አልደበቀም። “ ... መጀመሪያ፣ የግርማዊነትዎ ወደ ሱዳን መምጣት በእኛ በኩል ያልታሰበና ያልተጠበቀ አዲስ ነገር ነው። ሁለተኛ፣ በአሁኑ ሰዓት በሱዳን ያለው የታላቋ ብሪታንያ ጦር፣ ሱዳንን ለመጠበቅ የተዘጋጀ እንጂ፣ ከዚህ አልፎ ዘጠኝ መቶ ሺህ ወታደሮችና ሁለት መቶ የጦር አውሮፕላኖች ካሉት፣ የፋሽስት ኃይል ጋር ለመዋጋት አይደለም። እርግጥ ነው፣ ቀኑ መቼ መሆኑን ዛሬ ልነግረዎ ባልችልም፣ የታላቋ ብሪታንያ ጦር ከያለበት ተውጣጥቶ በኢትዮጵያ ላይ የሠፈረውን የፋሽስት ኃይል ለመደምሰስ የተቀረጠ ሐሳብ ያለው መሆኑ የሚያጠራጥር አይደለም። ይህንንም ድል እንደሚያገኝ ሳረጋግጥልዎ፣ የኢትዮጵያም ጉዳይ መታየት ያለበት ከዚህ ዕቅድ ጋር እንጂ፣ ተነጥሎ አለመሆኑን ልገልጽልዎ እወዳለሁ። ይሁን እንጂ፣ ግርማዊነትዎ በልዩ ልዩ አገሮች ያሉትን የኢትዮጵያን አርበኞች በማሰባሰብ ፋሽስትን ለመውጋት የሚያስችል ጦር ለማዘጋጀት፣ ሱዳን የመጣሁበት ዋና ጉዳይ ነው ብለዋል። ለዚህም ዕቅድዎ የሚያስፈልጉት መሣሪያዎችና መጓጓዣዎች እንዲሁም ስንቅና ለሎጂስቲክ የሚሆኑትን ሁሉ ከታላቋ ብሪታንያ በእርዳታ ለማግኘት ጠይቀዋል። በዚህ ጉዳይ እኔ የምሰጥዎ አስተያየት፣ እውነተኛውንና ትክክለኛውን ሁኔታ ነው። ዛሬ እዚህ ሱዳን ሆነን እንደምናየው፣ ይህን ሁሉ እርዳታ ለግርማዊነትዎ ለመስገስ የሚያስችል አቅም የለንም። ነገር ግን የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ካመነበትና ከወሰነ፣ የግርማዊነትዎን ጥያቄ በተግባር ለማዋል የሚያስቸግር ነገር ይኖራል ለማለት አልደፍርም። እኔ የምነግርዎ ወይም የማስረዳዎ፣ በእኔ ኃላፊነት ውስጥ የሚገኘውን በዚህ በሱዳን ክልል ውስጥ ያለውን ሁኔታ ብቻ ነው። መንግሥት ሲወስን ደግሞ መሣሪያዎቹ ከሌሎች ቦታ ሊሰበሰቡ ይችላሉ። ይህንንም ለመፈጸም አሁን ካለንበት ከዚህ ከሐምሌ ወር እንሥቶ እስከ መጭው ጥቅምት ወር 1940 ዓ.ም ድረስ መጠበቅ የሚያስፈልግ ይመስለኛል። በተጨማሪም ግርማዊነትዎ ለሚያደርጉት ዘመቻ አጠንክረው የጠየቋቸውን የቦንብ ጣይ አውሮፕላኖች፣ በእኛ ዘንድ ማግኘት አይችሉም። እኛ እዚህ ለመላው ሱዳን መጠበቂያ ያሉን የጦር አውሮፕላኖች ቁጥራቸው ከሦስት አይበልጥም። እኔ እስከዚህ ድረስ ገልጬ የማስረዳዎ፣ ግርማዊነትዎ በቶሎ ሊፈጸም የማይችል ተስፋ እንዳያደርጉ ነው። እንደሚያውቁት፣ የዓለም ጦርነት ተጀምሮ ገባንበት እንጂ፣ መውጫችን መቼ እንደሆነ አናውቀውም። ስለዚህ፣ በየዕለቱ የሚከሠተውን ሁኔታ እየተቋቋምን ለመጨረሻው ድል ለመብቃት ከመታገል በስተቀር ሌላ መንገድ የለንም .... ” አላቸው።

ከዚህ በላይ እንደታየው፣ የሱዳን ጠቅላይ ገዥ የተናገረውን ሁሉ ንጉሠ ነገሥቱ በጥሞና አዳምጠው የሰጡት መልስ፣ ሰር ስቲዋርት ሳይምስንን ሕሊና ሳይነካ አልቀረም። ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ አገረገዥው እውነተኛውንና ያለውን ሁኔታ ገልጸ ስላስረዳቸው ካመሰገኑት በኋላ፣ እሳቸውም በበኩላቸው የደረሰባቸውን ሁሉ በዝርዝር ያስረዱት እንደሚከተለው ነበር። “ ... ከሎንዶን ተነሥቼ ወደ ሱዳን ስመጣ፣ ከጠቅላይ ሚኒስትሩና ከጦር ሚኒስትሩ ቢሮ፣ የኢትዮጵያን ጉዳይ ከሚከታተሉት ዋና ዋና ሰዎች የተነገረኝ፣ የአገሬን ነፃነት ለማስመለስ ወደ አገሬ ዘልቄ ለማደርገው ዘመቻ፣ በጦር መሣሪያዎችም ረገድ ሆነ በሎጂስቲክ ማንኛውም እርዳታ ተዘጋጅቶ ይጠብቅዎታል የሚል ነበር። እኔም ይህን በቃል የተነገረኝን፣ በጽሑፍ ተገልጾ እንዲሰጠኝና በካይሮ እንዲሁም በሱዳን ላሉት የታላቋ ብሪታንያ ከፍተኛ የጦር መሪዎች፣ እኔው ራሴ በእጃቸው እንድሰጣቸው ብጠይቅ፣ ከሎንዶን ትዕዛዙ በቀጥታ ስለሚተላለፍላቸው አያስፈልግም ተባልኩ። ከሎንዶን ተነሥቼ እዚህ ከደረስኩ በኋላ፣ ወዲያውኑ እንደተገነዘብኩት፣ በሱዳን እንኳንስ ለዘመቻዬ

የሚያስፈልጉኝ የጦር መሣሪያዎች ተዘጋጅተው ሊጠብቁኝ ይቅርና፣ የእኔ ወደ ሱዳን መምጣት አስፈላጊነቱ ያልታመነበትና ያልተጠበቀም ሆኖ አግኝቼዋለሁ። እውነቱን ለመናገር ዛሬ ሱዳን ከደረስኩ በኋላ ያጋጠመኝን ሁሉ፣ ከሎንዶን ከመነሣቴ በፊት አውቄው ቢሆን ኖሮ፣ ሌላ መንገድ እፈልግ ነበር። በመሠረቱ፣ በሎንዶንና በሱዳን ባሉት የመንግሥት ኃላፊዎች መካከል በምንም ረገድ የአሠራርና የአስተያየት ልዩነት ይገጥመኛል ብዬ አልጠረጠርኩም። አሁን ወደ ኋላ መመለስ አይቻልም። ለአጋጠመን ችግር መድኃኒቱን ለማግኘት፣ ዛሬ ከአለንበት ወደፊት የምንራመደው እንዴት እንደሆነ ተነጋግረን መወሰን አለብን። ከዚህ ቀደም በላኩልዎ ማስታወሻ እንደገለጽኩት፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ የእኔን የንጉሠ ነገሥቱን ድምፅና መልዕክቴን በካርቱም ራዲዮ ከሰማበት ዕለት ጀምሮ፣ ልጁም አዋቂውም በያለበት ተንቀሳቅሶ፣ ጠላቱን ለመውጋትና ነፃነቱን ለማስመለስ ቆርጧል። ሕዝቤ የሚጠባበቀው፣ እኔ ንጉሠ ነገሥቱ የምሰጠውን መምሪያ ለመቀበልና በታዘዘበት ቦታ ተገኝቶ፣ በጠላቱ በፋሽስት ላይ ለመዝመት ነው። እንደሚያውቁት፣ የኢትዮጵያ ሕዝብ የፋሽስት መንግሥት ያደረሰበት ጭካኔና ግፍ ወደር የሌለው ስለሆነ፣ ለነፃነቱ መሥዋዕትነትን ለመቀበል የሚያመነታ አይደለም። የእኔን ወደ ሱዳን መምጣትና የታላቋ ብሪታንያም መንግሥት በሚሰጠን እርዳታ፣ ጠላትን ለመደምሰስ መወሰናችንን በካርቱም ራዲዮ በአማርኛ ቋንቋ ከተነገረው በኋላ፣ እስከ ዛሬ ድረስ አንዳች እርምጃ ሳንወስድ ጊዜውን በማቃጠላችን፣ ተስፋውን ቆርጦ እንዳይበተን ከፍ ያለ ሥጋት አድሮብኛል። ጠላታችን ፋሽስትም እኛ ድምፃችንን በማጥፋታችን፣ ሰላም አገኘሁ በማለት፣ የመከላከያ ኃይሉን የበለጠ ለማጠንከር እንደሚመቸው መገመት አለብን። እርስዎ እንደነገሩኝ፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት እኔ የጠየቅኩትን የጦር መሣሪያ አሟልቶ ለመስጠት የሦስትና የአራት ወራት ጊዜ የሚጠይቀው ቢሆንም፣ እስከዚያው ድረስ፣ በኢትዮጵያ ግዛት ውስጥ ያሉት ተዋጊዎቹ አርበኞቹና በጐረቤት አገሮች በኬንያና በሱማሌ የሚገኙት ስደተኞች፣ በሱዳን ውስጥ አንድ አማካይ በሆነ ቦታ እንዲሰበሰቡና የዘመቻ ሥልጠና እንዲሰጣቸው ቢደረግ፣ ትልቅ ውጤት እንደምናገኝበትሙሉ ዕምነት አለኝ። ስለዚህና ስለሌሎቹም ዋና ዋና ጉዳዮች እኔው ራሴ ካይሮ ሄጄ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ ከሆኑት ከጄኔራል ኧርል ዌቭል (Earl Wavell) መነጋገር ስለምፈልግ፣ ቀጠሮው በእርስዎ ቢሮ በኩል ቢዘጋጅልኝ ከልብ አመሰግናለሁ ... "
ሲሉ ንጉሠ ነገሥቱ ሐሳባቸውን ደመደሙ።

የሱዳን ጠቅላይ ገዥ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በዝርዝር የገለጹለትን አስተያየት ካደመጠ በኋላ፣ በንጉሠ ነገሥቱ ላይ እሱ ራሱና የጦሩ አዛዥ ጄኔራል ፕላት የፈጸሙት ሁሉ ምን ያህል አሳዛኝ መሆኑ ስለተሰማው፣ ጃንሆይ ካይሮ ለመሄድ የጠየቁትን ቀጠሮ እንደሚያዘጋጅላቸውና፣ እስከዚያም ድረስ የእሱ ሥልጣን የሚፈቅደውን ሁሉ እንደሚፈጽምላቸው ቃል ሰጥቶ በደህና እኪኋን ሸኛቸው።

ጃንሆይ አገረ ገዥውን አነጋግረው ወደ ማረፊያቸው ወደ ጀበል አውልያ እንደተመለሱ፣ ረዳቶቻቸው አቶ ወልደጊዮርጊስ ወልደዮሐንስና አቶ ሎሬንሶ ታዕዛዝ የሚከተለውን ሐሳብ አቀረቡላቸው። ግርማዊነትዎን በምክርና በመገናኛ ዘዴዎች እንዲረዳ ከእንግሊዝ መንግሥት ተመድቦ የመጣው ቻፕማን አንድርውስ፣ የሱዳን አገረ ገዥና የጦሩ አዛዥ በጃንሆይ ላይ የሚፈጽሙትን በደል፣ ለጠቅላይ ሚኒስትሩ ለሚስተር ቸርችል በቀጥታ በቴሌግራም እንዲያስታውቁ ደጋግሞ መናገሩ ይታወሳል። ጃንሆይም ይህንን ሐሳብ ወዲያውኑ ፈቅደው እንዲፈጸም ያላዘዙት፣ ጥቂት ጊዜ በትዕግሥት ጠብቆ የመጨረሻውን ሁኔታ ማየት ይሻላል በማለት ነው።

አሁን መጨረሻው ሁኔታ ላይ የደረስን መስሎናል፡፡ ዛሬ የሱዳን አገረገዥ የነገሩዎትን በጥንቃቄ ካጠናነው በኋላ፤ ከዚህ ቀደም ሚስተር ቻፕማን እንደመከረን ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል ጃንሆይ በቴሌግራም ንጉሣዊ መልዕክትዎን እንዲያስተላልፉ አስፈላጊ መሆኑን አምነንበታል፡፡ እነዚህ በሱዳን ያሉት የታላቋ ብሪታንያ ባለሥልጣኖች ለግርማዊነትዎ የገለጹት፤ " ... **እንኳንስ ግርማዊነትዎ ለሚመራው ዘመቻ አስፈላጊውን የጦር ትጥቅ አዘጋጅተን ለመጠበቅ ይቅርና፤ የግርማዊነትዎን ከሎንደን ወደ ሱዳን መምጣት እንኳ አልተነገረንም** ... " ብለዋል፡፡ ይህ የሚሉት እውነት መሆኑና አለመሆኑ መታወቅ አለበት፡፡ ስለዚህም ዛሬውኑ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችል በቴሌግራም ማስታወቁ የተገባ ነው እንላለን ሲሉ፤ አቶ ወልደጊዮርጊስና አቶ ሎሬንሶ አስተያየታቸውን አቀረቡላቸው፡፡

ንጉሠ ነገሥቱ የሁለቱን ረዳቶቻቸውን ሐሳብ ካዳመጡ በኋላ የሚከተለውን መለሱላቸው፡፡ " ... **የሱዳን አገረ ገዥ በመጨረሻ ስንሰነባበት የተናገረው አንድ ነገር አለ፡፡ የጃንሆይን ችግር ስለተረዳሁት፤ በእኔ ሥልጣን ማድረግ የምችለውን ሁሉ አደርጋለሁ** ... " ብሏል፡፡ ይህ የሰጠው ቃል እስከምን ድረስ እንደሆነ ለማስጨረስ አንድ ዕድል መስጠቱ አስፈላጊ ይመስለናል፡፡ በዚሁ ጊዜ ውስጥ ግን፤ ለእንግሊዝ ሕዝብና መንግሥት አንድ መልዕክት በስማችን ተዘጋጅቶ፤ በቢ.ቢ.ሲ ራዲዮና በሎንደን ጋዜጦች እንዲወጣ ቢደረግ፤ ትላቅ ጥቅም ሊሰጥ ይችል ይሆናል ብለን አስበናል፡፡ ይህም መልዕክት ዛሬ ያለንበትን ሁኔታና በተስፋም የምንጠብቀው ምን እንደሆነ የሚገልጽ ስለሚሆን፤ በሌላ መንገድ ደግሞ በታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ ዘንድ የአቤቱታ ድምፅ እንደማሰማት ሊገመትልን ይችላል፡፡ ስለዚህ፤ እናንተም (ወልደጊዮርጊስና ሎሬንሶ) ከአማካሪያችን ከቻፕማን አንድርውስ ጋር ሆናችሁ ብታጠኑትና ረቂቁን አዘጋጅታችሁ ብታቀርቡልን ማለፊያ ይሆናል ሲሉ መምሪያ ሰጡ፡፡

እንደሚታየው፤ ጃንሆይ በሱዳን ያሉት የእንግሊዝ ባለሥልጣኖች የሚፈጽሙባቸውን በደል በቀጥታ ለቸርችል ማመልከትና ማጋለጥ አልፈለጉም፡፡ የእሳቸው አስተያየት፤ ከሱዳን አገረገዥና ከጦሩ አዛዥ ጋር በዚህ አኳኋን ተጣድፎ መጣላቱ ምንም ዓይነት ፍሬ ሊሰጥ ስለማይችል፤ ጥቂት ጊዜ ታግሶ ሁኔታው ሲያመችና ሌላም አማራጭ አለመኖሩ ሲታወቅ፤ ለጠቅላይ ሚኒስትሩ ማመልከት ይሻላል የሚል ነው፡፡ ይህንን አቋማቸውን ለማስለወጥ ረዳቶቻቸው ብዙ ሞክረው ስላልቻሉ፤ እሳቸው በፈለጉት መሠረት ለቢ.ቢ.ሲ ራዲዮና ለየጋዜጦቹ ተዘጋጅቶ የተላለፈው መልዕክት የሚከተለው ነበር፡፡

" ... **እኔ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት በዚህ መልዕክት የምገልጸው ሐሳብ፤ ለታላቋ ብሪታኒያ ሕዝብና መንግሥት እንዲደርስልኝ እጠይቃለሁ፡፡**

**በፋሽስት ጣልያን በግፍ የተወረረችውን አገሬን ለማስለቀቅና ነፃነቷን ለማስመለስ፤ ካለፉት አራት ዓመታት ጀምሮ ያለማቋረጥ፤ ጠላትን አስጨንቀው ሲዋጉ የቆዩትን አርበኞቼን አስተባብሬ፤ ከታላቋ ብሪታንያ መንግሥት በሚሰጠኝ የጦር እርዳታ በፋሽስት ላይ ለመዝመት በሱዳን እገኛለሁ፡፡ ይህንንም ዓላማዬን ከግቡ ለማድረስ ከሎንደን ከመነሣቴ ካለፈው አንድ ወር በፊት፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የሰጠኝን ቃል በተቻለ ፍጥነት እንደሚያስፈጽምልኝ ከፍ ባለ ተስፋና ትዕግሥት እጠብቃለሁ፡፡**

ከሎንዶን ተነሥቼ ሱዳን እንደደረስኩ በካርቱም ራዲዮ ለኢትዮጵያ ሕዝብ ባሰማሁት ቃል፤ የታላቋ ብሪታኒያ መንግሥት በሚሰጠኝ የጦር እርዳታ፤ ጠላትን ለማባረር ዘመቻውን እየመራሁ ወደ እርሱ ለመምጣት በዝግጅት ላይ መሆኔን አስታውቂያለሁ። የኢትዮጵያ ሕዝብ፤ የንጉሠ ነገሥቱን የምሥራች ድምፅና የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የሚያደርግለትን እርዳታ በመስማቱ፤ ከመጠን በላይ ተደስቶ በሚሰጠው መምሪያ መሠረት ጠላቱን ለመውጋትና መሥዋዕትነትን ለመቀበል ቆርጦ ተነሥቷል።

በኢትዮጵያ ሕዝብ ላይ የፋሽስት የግፍ አስተዳደር ከወደቀበት ካለፉት አራት ዓመታት ጀምሮ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥትና ሕዝብ፤ እኔን ንጉሠ ነገሥቱን ተቀብሎ በማስተናገድ የለገሠውን ውለታ፤ የኢትዮጵያ ሕዝብና ታሪክ ምን ጊዜም ሲያስታውሱት ይኖራሉ። ይኸ ዛሬ የጋራ ጠላታችን የሆነው የፋሽስት መንግሥት፤ የኢትዮጵያን ሕዝብ በጭካኔ እየጨረሰ አገሩን በሙሉ በእጁ አስገብቼዋለሁ በማለት በፕሮፓጋንዳ ቢፎክርም፤ የኢትዮጵያ ግዛት በሙሉ በጠላት እጅ አለመውደቁ ተመስክሮበታል። እኔም ንጉሠ ነገሥቱ ከዙፋኔ ፈጽሞ ያልወረድኩና የክብር ስሜን ያልለቀቅኩ መሆኔን ማረጋገጥ እወዳለሁ። በዚህም አጋጣሚ ከዛሬ አራት ዓመታት በፊት የተናገርኳትን ቃል ማስታወስ እፈልጋለሁ። " ... በዚህ ዓለም ፍርድ ካለ፤ በእግዚአብሔር ፈቃድና ቸርነት በዙፋኔ ላይ እንደገና እመለሳለሁ ... " ብዬ ነበር። አሁንም በእግዚአብሔር ፈቃድና በታላቋ ብሪታንያ እርዳታ፤ በሕዝቤ ብርታትና መሥዋዕት ተቀባይነት የተናገርኳት ቃል የምትፈጸምበት ቀን ዛሬ ናት ብዬ አምናለሁ። የአምላክ ቸርነት ሆኖ ለጋራ ደስታችን ያብቃን እያልኩ፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ ፍጹም ወዳጅና ረዳት ለሆነው ለታላቋ ብሪታንያ ሕዝብና መንግሥት ልባዊ ምኞቴን እገልጻለሁ።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ
ንጉሠ ነገሥት

ይህ መልዕክት በሚገባ ተዘጋጅቶ በቢቢሲ ራዲዮና በታወቁት የሎንዶን ጋዜጦች፣ ከመልካም አስተያየት ጋር እየተደገፈ በመገለጹ፤ አንደኛ/ የጠቅላይ ሚኒስትሩና የጦር ሚኒስትሩ ጽሕፈት ቤቶች ዓይነተኛ የሆነ መልካም ግምት አሳርፈውበታል። ሁለተኛ/ ንጉሠ ነገሥቱም ያሰቡት ስለተፈጸመላቸው የደስታ ስሜት አድሮባቸዋል።

**Reference:** a/ FO-371 27516
b/ Report of Chapman-Andrews

# ምዕራፍ ፫

## ቀ.ኃ.ሥ ከዌቨል ጋር

ቀደም ሲል እንደተጠቀሰው የሱዳን አገረ ገዥ ሰር ስትዋርት ሳይምስ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ተቀብሎ ካነጋገራቸው በኋላ፤ በፊት ከነበረው የጨለመ አስተያየት ወደ ቀና መንገድ ማዘንበሉ ታይቷል። በውይይቱ መጨረሻ ላይ፤ " ... **ግርማዊነትዎ ጥቂት ጊዜ ቢታገሡኝ፤ በእኔ ሥልጣን የምችለውን ሁሉ አደርግልዎታለሁ** ... " ሲል በሰጣቸው ቃል መሠረት፤ በመጀመሪያ የወሰደው እርምጃ፤ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ የሆነው ጄኔራል ኧርል ዌቨል (Earl Wavell) ከካይሮ ወደ ካርቱም ሲመጣ፤ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን ተቀብሎ እንዲያነጋግራቸው ቀጠሮውን ማዘጋጀት ነበር።

ጄኔራል ዌቨል ንጉሠ ነገሥቱን የሚያያቸው ለመጀመሪያ ጊዜ ስለነበረ፤ በፊልድ ማሬሻል ወታደራዊ ልብሳቸው፤ ቀበቶ ታጥቀውና ቱራዥር አንዠርግገው ሲቀበላቸው፤ በመንፈስ ንቃታቸውና በፐርሰናሊቲያቸው የተለየ አክብሮትና አስተያየት አደረበት። ምንም እንኳ ንጉሠ ነገሥቱ <u>ሳይጠበቁ</u> በድንገት ሱዳን መምጣታቸውና ከዚያም በኋላ ያለውን ሁኔታ እነ ጄኔራል ዊሊያም ፕላት ሪፖርት ያቀረቡለት ቢሆንም፤ ጃንሆይ ራሳቸው የመጡበትን ጉዳይና ያጋጠማቸውን ችግር እንዲነግሩት ለመስማት መዘጋጀቱን ገለጸላቸው። በዚህም መሠረት ንጉሠ ነገሥቱ የሚከተሉትን ጉዳዮች አብራርተው አስረዱት።

" ... ከሎንዶን ተነሥቼ ወደ ካርቱም ስጓዝ፤ **በመጀመሪያ ካይሮ ላይ ቆሜ የመጣሁበትን ጉዳይ ከእርስዎ ጋር ለመነጋገር ፈቃዱ ብቻ ሳይሆን ብርቱ ፍላጉቴም ነበር።** ነገር ግን፤ በሱዳን ያሉት አገረገዥውና የጦሩ አዛዥ፤ **ስለ ኢትዮጵያ ንጉሠ ነገሥት ወደ ካርቱም መምጣት ከሎንዶን የተነገረን ስለሌለ፤** በተጨማሪም ለፀጥታው አጠባበቅ ካርቱም የተመቸ ቦታ ስላልሆነ፤ በቀጥታ ወደ ዋዲ ሐልፋ ሄደው በዚያ እንዲያርፉ ይሁን ሲሉ፤ ለአውሮፕላኑ አዛዥ ትዕዛዝ ስለሰጡ፤ **"ዋዲ ሐልፋ" ሄጄ በዚያ በረሃማ ቦታ ለብዙ ቀናት ተዘግቶብኝ ስነበትኩ።** በዚሁ ጊዜ፤ እኔን በአማካሪነት እንዲረዳ ተመድቦ አብሮኝ ያለው **ሚስተር ቻፕማን አንድርውስ፤** የደረሰብኝን ችግር ለሱዳን ባለሥልጣኖች በማስረዳት በብዙ ስለታገለ፤ **ከዋዲ ሐልፋ ወደ ካርቱም አካባቢ መጥቼ፤ "ጀበል አውልያ" በተባለው ቦታ የተሻለ ማረፊያ ተሰጠኝ።** ከዚያም በሚስተር ቻፕማን አንድርውስ ጥረት፤ በመጀመሪያ የጦሩን አዛዥ ጄኔራል ዊሊያም ፕላትን፤ ቀጥሎም አገረገዥውን ሰር ስትዋርት ሳይምስን ለማነጋገር ቻልኩ። በመሠረቱ፤ ሁለቱም ባለሥልጣኖች የእኔን ወደ ካርቱም መምጣትና የመጣሁበትም ጉዳይ ለምን እንደሆነ ከሎንዶን ከጠቅላይ ሚኒስትሩ ወይም ከጦር ሚኒስትሩ የተላለፈልን ትዕዛዝ ስለሌለ፤ የምናውቀው ነገር የለም የሚል አቋም የያዙ ናቸው። እኔ ደግሞ፤ ከጠቅላይ ሚኒስትሩና ከጦር ሚኒስትሩ ጽሕፈት ቤቶች ስለ ኢትዮጵያ ጉዳይ ኃላፊዎች ከሆኑት ሰዎች ጋር በሰፊው ተነጋግሬ፤ በፋሽስት ላይ ለመዝመት ያለኝንም ፕላን አቅርቤ ከተስማማን በኋላ፤ አስፈላጊው ትራንስፖርት ተዘጋጅቶልኝ በምክር የሚረዳኝም ሰው ተመድቦልኝ በሥርዓት የመጣሁ ነኝ። ስለዚህም፤ እኔን በጣም ያስገረመኝ በሱዳን

ያሉት የታላቋ ብሪታንያ ባለሥልጣኖች እነሱ እንደሚሉት ከሎንደን ምንም ዓይነት ትዕዛዝ ባይደርሳቸውም፤ የአንድ የታወቀ አገር ንጉሠ ነገሥት እንደመሆኔ መጠን፤ ወደ ካርቱም የመጣሁበትን ጉዳይ ሎንደንን ጠይቀው ማወቅ ይችሉ ነበር። እኔ እንደተረዳሁትና እንደመሰለኝ፤ በሱዳን ያሉት ባለሥልጣኖች የእኔን መምጣት ከዚያም በላይ ወደ አገሬ ወደ ኢትዮጵያ ለሚዘጋጀው ጦር የእኔን አስፈላጊነት የማይቀበሉ በመሆናቸው፤ ከሎንደን የተሰጠን መምሪያ የለም በሚል ሰበብ፤ ምንም ነገር መሥራት እንዳልችል ዘግተውብኝ ሰንብተዋል። እኔ ግን ሱዳን ከመጣሁ ጀምሮ የደረሰብኝን ችግር ሁሉ በመዘርዘር፤ ለጠቅላይ ሚኒስትር ቸርችልና ለጦር ሚኒስትር ኤደን በቴሌግራም ማስታወቅ ስችል አላደረግኩም። ይህንንም እርምጃ ያልወሰድኩት፤ በሁለት ምክንያቶች ነበር። አንደኛ፤ የአገሬን ነፃነት ለማስመለስ ያለብኝን ከፍተኛ ኃላፊነት ለማከናወን ሥራዬን የምጀምረው በሰላም እንጂ፤ በጠብ መሆን የለበትም ብዬ ስለማምን ነው። ሁለተኛ፤ በሱዳን ያሉት ባለሥልጣኖች በእኔ ላይ የሚያደርጉት ሁሉ ትክክል አለመሆኑን ራሳቸው ተረድተው ከመግባባት ደረጃ ልንደርስ እንችል ይሆናል የሚል ተስፋ በማሳደር ነው። እንደጠቀስኩልዎ፤ አሁን በቅርቡ ሁለቱንም ባለሥልጣኖች አነጋግሬአለሁ። የጦሩ አዛዥ ጄኔራል ፕላት፤ የእኔን ወደ ሱዳን መምጣት ሆነ፤ ወደፊትም በፋሽስት ላይ ለመዝመት የማስበውን ያልተቀበሉት መሆናቸውን በአኳኋናቸው ከማስማት በስተቀር ቀና የሆነ አስተያየት አልሰጡኝም። አገረ ገዥው ሰር ስትዋርት ሳይምስ ግን፤ ረዘም ያለ ጊዜ ሐሳብ ለመለዋወጥ ፈቃደኛ ከመሆናቸው በላይ፤ በንግግራችን መጨረሻ ላይ " ... የእኔ ሥልጣን የሚፈቅድልኝን ሁሉ እረዳዎታለሁ ..." በማለት፤ የመግባባት መንፈስ አሳይተውኛል። ለምሳሌም ያህል ዛሬ ከእርስዎ ጋር ለመነጋገር እንድችል ቀጠሮውን ያዘጋጁልኝ እሳቸው በመሆናቸው፤ ላመሰግናቸው እወዳለሁ። " ዛሬ እኔ ከእርስዎ ጋር ለመነጋገር የምፈልጋቸው ዋና ዋና ጉዳዮች የሚከተሉት ናቸው።

- ወደ ሱዳን ስመጣ ያቀድኩት ፕሮግራም፤ የታላቋ ብሪታኒያ መንግሥት በሚሰጠኝ እርዳታ፤ በኢትዮጵያ ውስጥ ያሉትን ተዋጊ አርበኞችና እንዲሁም በሱዳንና በኬንያ፤ በጂቡቲና በሱማሊያ የሚገኙትን ስደተኞች አሰባስቤ ጦር በማዘጋጀት፤ የክረምቱ ወራት ሳይገባ (ሐምሌና ነሐሴ) አገሬን በወረረው ፋሽስት ላይ ዘመቻዬን ለመጀመር ነበር። ነገር ግን ቀደም ብዬ እንደነገርኩዎ ሱዳን እንደደረስኩ፤ በመጀመሪያ በዚያ እጅግ በረሃማ በሆነው በ "ዋዲ ሐልፋ" ቀጥሎም ከካርቱም ውጭ ጀበል አውልያ በተባለው ሥፍራ እንድቀይ ተዘግቶብኝ፤ ምንም ነገር ለመሥራት ሳልችል እስካሁን ቆይቻለሁ። ከደረሱብኝ ሁኔታዎች ጋር በማመዛዘን እንደተረዳሁት፤ ምንጩ ከየት እንደሆነ ባላውቀውም፤ ወደ ሱዳን የመጣሁበትን ጉዳይ ለማሰናከል ታጥቆ የሚሠራ ወገን ያለ ይመስለኛል። ለዚህም ምሳሌ የሚሆኑ አንዳንዶቹ ሁኔታዎች የሚከተሉት ናቸው።

1. በኢየሩሳሌምና በግብፅ በስደት ከሚኖሩት ኢትዮጵያውያን መካከል ለምክርም ሆነ ለአንዳንድ ሥራዎች ሊረዱኝ የሚችሉትን መርጬ ወደ እኔ እንዲመጡ የመግቢያ ፈቃድ (ቪዛ) ለጠየቅኩላቸው ሰዎች እስካሁን መልስ አልተሰጠኝም።

2. የእኔን መምጣት ሰምተው ወደ ሱዳን እየገሰገሡ የገቡት ኢትዮጵያውያን አርበኞችና ስደተኞች፤ ዝርዝራቸው ተመዝግቦ የጦር ሥልጠና እንዲሰጣቸው ያቀረብኩት ጥያቄ እስካሁን ውሳኔ አልተሰጠውም።

3. በአገር ፍቅር ስሜት ተቀስቅሰው፣ የኢትዮጵያ ጠላት የሆነውን ፋሽስትን ለመውጋት ኬንያ ላይ የተሰበሰቡት ቁጥራቸው እስከ ስድስት መቶ የሚደርስ የኤርትራ ተወላጆች፣ ወደ እኔ ለመምጣት ፈቃድ ቢጠይቁ የኬንያው ገዥ ከልክሉ አግዷቸዋል። ስለዚህም ፈቃዱ እንዲሰጣቸው በቴሌግራም ደጋግሜ ባመለክት፣ እስካሁን መልስ አላገኘሁም።

4. ቁጥራቸው እስከ አንድ ሺህ የሚደርስ፣ በጂቡቲ፣ በሐርጌሳና በገዳሪፍ ላይ የሚገኙት ኢትዮጵያውያን ስደተኞች፣ ወደ እኔ መጥተው ለዘመቻው ዝግጅት ለማድረግ የጠየቁት የመግቢያ ፈቃድ ስላልተሰጣቸው፣ በመጠባበቅ ላይ ይገኛሉ። ከእነዚህ ሰዎች መካከል ብዙዎቹ የእኔ የክብር ዘበኞቼ የነበሩ በመሆናቸው፣ በጣም አስፈላጊዎች መሆናቸውን በመግለጽ ፈቃዱ እንዲሰጣቸው ላመለከትኩት እስከአሁን መልስ አልተሰጠኝም።

5. ጠላትን ለማዳከም ፍቱን ነው ተብሎ የታመነበትን የፕሮፓጋንዳ ሥራ ለማካሄድ፣ ከእኔ በኩል አዋቂዎች ተመድበው ብዙ ዝግጅት ተደርጐ ነበር። ነገር ግን የተዘጋጁትን ጽሑፎች በአውሮፕላን ለመበተን ተጠይቆ፣ የሚቻል ወይም የማይቻል አለመሆኑ መልስ አልተሰጠበትም።

እንግዲህ! እንደሚያዩት እኔ የጠየቅኩት፣ በመጀመሪያ ደረጃ የጦር መሣሪያዎች እንዲሰጡኝ ሳይሆን፣ ለዘመቻው የማስልፋቸውን አርበኞችና ተዋጊዎች ለማሰባሰብና አሠልጥኖ ለማዘጋጀት ነው። በሱዳን ያሉት ባለሥልጣኖች ግን በቅድሚያ የሰጡኝ መልስ፣ እኛ እዚህ ያለነው ሱዳንን ለመጠበቅ ስለሆነ፣ በኢትዮጵያ ያለውን ፋሽስትን ለመውጋት የሚያስችል ድርጅትም መሣሪያም የለንም የሚል ነው። እኔ ተዋጊዎቼን ሳላዘጋጅ የጦር መሣሪያዎች ይሰጠኝ አላልኩም። እስከዚህም ድረስ የተሳሳተ ወይም የሚታረም ሐሳብ ያለኝ ሰው አይደለሁም። የምድር ጦር መሣሪያዎቹንና የአየር ኃይሉን ጉዳይ፣ ከሁሉ አስቀድሞ የተዋጊዎቹ ዝግጅት ከተጠናቀቀ በኋላ፣ መጀመሪያ ከእርስዎ ጋር ቀጥሎም እንደአስፈላጊነቱ ከጠቅላይ ሚኒስትሩም ሆነ ከጦር ሚኒስትሩ ጋር እኔው ራሴ ለመነጋገር ያሰብኩበት ጉዳይ ነበር። ነገር ግን በሱዳን ያሉት ባለሥልጣኖች ለዘመቻዬ የሚያስፈልጉኝን መሠረታዊ ጉዳዮች በቅደም ተከተል እያጠኑ፣ እርዳታቸውን በመለገስ ፋንታ በራቸውን እየዘጉ ሊያስቸግሩኝ አይገባም። ለርስዎ ምንም አልደብቅዎትም። እኔ የቆረጥኩ ሰው ነኝ። ለአገሬ ነፃነት አገሬ ገብቼ ከሕዝቤ ጋር መሞትን የመረጥኩ ነኝ። ስለዚህ፣ ያለሁበትን ሁኔታና የሚያስፈልጉኝንም ጉዳዮች ዘርዝሬ ነግሬዎታለሁ። የምጠይቀውን ከሟላችሁልኝ ዘመቻዬን መጀመር የምመኘው ከነሐሴ 15 ጀምሮ ነው። ለሚቻለውና ለማይቻለው መልሱ የርስዎ ፋንታ ነው ... " ሲሉ ንጉሠ ነገሥቱ አቋማቸውን አስረዱ።

## የዌቨል መልስ

ግርማዊነትዎ፣ የአገርዎን ነፃነት ለማስመለስ ወደ ሱዳን የመጡበትን ጉዳይና ያጋጠምዎትን ችግር ዘርዝረው ስለአስረዱኝ ከልብ አመሰግንዎታለሁ ካለ በኋላ፣ የታላቋ ብሪታንያ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ ጄኔራል ኧርል ዌቨል በበኩሉ ለንጉሠ ነገሥቱ የገለጹላቸው የሚከተለውን ነበር።



ብሪታንያ የመካከለኛው ምሥራቅ ጦር ዋና አዛዥ ጄኔራል ኧርል ዌቨል፤

" ... ግርማዊነትዎ የሚያውቀው ነው ብዬ እገምታለሁ። እስከ አለፈው ሚያዝያ ወር 1940 ዓ.ም ድረስ፤ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት ሙሶሊኒ ከሒትለር ጋር ሆኖ ጦርነቱ ውስጥ ይገባል ብሎ አላሰበም ነበር። ምናልባት፤ የፋሽስት መንግሥት በድንገት ተነሥቶ ጦርነቱ ውስጥ ገብቶ የወጋን እንደሆነ፤ የእኔ ኃላፊነት በሆነው በመካከለኛው ምሥራቅ በኩል መዘጋጀት አያስፈልገኝም ወይ? ብዬ የበላዮቼን ጠይቄ ነበር። ዋናው ሐሳባችን በምዕራቡ ክፍል ነው እንጂ የምሥራቁ አይደለም የሚል መልስ ተሰጠኝ። ወዲያው ጦርነቱ እንደተፋፋመ፤ ፈረንሣይ ባልተጠበቀ ፍጥነት ድል ሆና በመውደቋ፤ ሁኔታዎቹ ሁሉ ተለዋወጡ። ጦርነቱም ምዕራብ ላይ ስለአተኮረ፤ በእኔ ዘንድ የተከላካይ ጦር አዘጋጀሁ እንጂ፤ የአጥቂ ጦር ማቋቋም አልቻልኩም። ግርማዊነትዎ እንደሚያውቀው፤ ከሁለት ዓመታት በፊት የፋሽስት መንግሥት ከታላቋ ብሪታንያ ጋር በመሠረተው ወዳጅነት ምክንያት፤ የኢትዮጵያ ይዞታውን እንግሊዝ እንዲያውቅለት በማስደረጉ፤ የኢትዮጵያ ሕዝብ ከፋሽስት ጋር ለሚያደርገው ትግል እንዳች እርዳታ እንዳንሰጥ ከሎንዶን ታዘን ነበር። ይህ ትዕዛዝ ጣልያን ጦርነቱ ውስጥ ከገባች በኋላ የተሰረዘ ስለሆነ፤ ኮሎኔል ሳንድፎርድ የተባለውን የኢትዮጵያ ወዳጅ፤ በኢትዮጵያ ጉዳይ የእንግሊዝ ሚሲዮን ኃላፊ እንዲሆን መድቤ፤ ቁጥራቸው የተወሰኑ መሣሪያዎችና ጥቂት ገንዘብም ጭምር ለተዋጊዎቹ አርበኞች እንዲደርስ አድርጌያለሁ። ከዚህም በቀር፤ ኮሎኔል ሳንድፎርድ በጃንሆይ ስም እያደረገ ያስበተናቸው የፕሮፓጋንዳ ጽሑፎች፤ ሕዝቡን ለማነቃቃትና ወደ ተስፋ እንዲያዘነብል አስደርጓል። እኔ ይህንን የምጠቅስልዎ እስካሁን የተደረገው እርዳታ ብዙ ወይም በቂ ነው ለማለት አይደለም። መጠነኛም ቢሆን ለኢትዮጵያ ሕዝብ መልካም ሐሳባችንና ምኞታችን የማያቋርጥ መሆኑን ለማመልከት ነው።

የፋሽስት መንግሥት የጋራ ጠላታችን ከሆነ በኋላ፤ ግርማዊነትዎ ታላቋ ብሪታንያ በምታደርግልዎ እርዳታ የአገርዎን ነፃነት ለማስመለስ ወደ ሱዳን የሚመጡት እንደዚህ በተፋጠነ ሁኔታ ይሆናል ብዬ እኔም አልጠበቅኩም ነበር። በእውነቱም መምጣትዎን ስሰማ ሳልደነቅ አልቀረሁም። ምክንያቱም፤ ምንም ዓይነት ድርጅት ተዘጋጅቶ እንዳልጠበቀዎ ስለማውቅ ነው። በሱዳን ያሉትም አገረገዥውም ሆኑ የጦሩ አዛዥ፤ የግርማዊነትዎን መምጣት አለመስማታቸው የሚታመን ነው። ለእኔም መረጃው የደረሰኝ፤ የግርማዊነትዎን ወደ ካርቱም ጉዞ መጀመር እንጂ፤ ሌላ በተጨማሪ የተገለጸልኝ የለም። እንዲሁም፤ የዘመቻ ፕላን (Plan D'Action) አዘጋጅተው ሎንዶን ላሉት ባለሥልጣኖች ማቅረብዎን አልሰማሁም።

የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት አገርዎን ኢትዮጵያን ከፋሽስት ይዞታ ለማስለቀቅ እርምጃ እንደሚወስድ ጥርጥር የለውም። ይሁን እንጂ፤ በፋሽስት ላይ የሚደረገው ዘመቻ በምን አኳኋን መከናወን እንዳለበትና ለግርማዊነትዎም የሚሰጠው እርዳታ፤ ምንና ምን እንደሆነ ከመንግሥት ተወስኖ የሚላክልንን መምሪያ መጠበቅ አለብን። ይህንንም ስል፤ ለዋና ዋናዎቹ መሠረታዊ ጉዳዮች ለምሳሌ፤ እንደ ጦር መሣሪያዎች ለመሳሰሉት እንጂ፤ ለዝግጅቱ እኛ የምንችለውን ሁሉ ከማድረግ ወደ ኋላ አንልም። በተለይ በጦር መሣሪያዎች ረገድ ያሉትን ችግሮች መቼ ሊወገዱ እንደሚችሉ ቢጠይቁኝ፤ ከፊታችን መስከረም እስከ ኅዳር ወር ድረስ ባለው ጊዜ ውስጥ ሊሆን ይችላል ከማለት በስተቀር፤ የተቆረጠ ቀን ልነግርዎ አልችልም። አሁን ካለንበት ከሐምሌ ወር እስከ ኅዳር ድረስ ያለው ጊዜ ይህን ያህል ሩቅ አይደለም። በእኔ አስተያየት ጃንሆይ ወደ ኢትዮጵያ የሚያደርጉት ዘመቻ መፋጠን የለበትም። ምክንያቱም፤ በኢትዮጵያ የተከማቸው የፋሽስት የጦር

ኃይል ምንም አልተካም። ይህ ጦር ቁጥራቸው እስከ አንድ ሚሊዮን ለሚገመቱ ወታደሮች ሙሉ ትጥቅ ያለው መሆኑን ጃንሆይ ሳይሰሙት አልቀሩም። ስለዚህ፣ ዝግጅትዎ በሚገባ ሳይሟላ ዘመቻውን ለመጀመር መፋጠን ብዙ አደጋ ሊያስከትል ይችላል ብዬ እሠጋለሁ። ግርማዊነትዎ እንደሚረዳው፣ በሁለት ወር ውስጥ ፈጥኖ በመዝመት ድል ከመሆን፣ ስድስት ወራት ጠብቆ ድልን መጉናጸፍ ብዙ ሺህ ጊዜ የተሻለ ይሆናል። እርግጥ ነው! ወደ ኢትዮጵያ የሚደረገው ዘመቻ ከተጓተተ ወይም ጊዜ የሚፈጅ ከሆነ፣ ጠላት የመከላከያ ኃይሉን የበለጠ ለማጠናከር ዕድል አያገኝም ወይ? በማለት ግርማዊነትዎ የሚሠጉ መሆንዎን ሰምቻለሁ። እኔ በጦር መሪነቴ የማውቀውንና የማምነውን ልገልጽልዎ እፈልጋለሁ። ፋሽስት ከውጭ መሣሪያዎች አምጥቶ ኃይሉን የበለጠ ለማጠናከር እንዳይችል መንገዶች ሁሉ ስለተዘጉበት፣ ዛሬ ካለበት ሁኔታ አንድ እርምጃ እንኳ መጨመር አይችልም። ስለዚህም፣ ግርማዊነትዎ ያደረበት ሥጋት መወገድ ይኖርበታል።

ቀደም ብዬ እንደገለጽኩልዎ፣ በፋሽስት ላይ ለሚደረገው ለትልቁ ዘመቻ፣ አስፈላጊውን ትጥቅና መሣሪያዎች ለማዘጋጀት፣ የታላቋ ብሪታንያ መንግሥት የሚሰጠንን ውሳኔና መምሪያ መጠበቅ አለብን። እስከዚያም ድረስ ለአንዳንድ ዝግጅት በእኛ በኩል መከናወን ያለበትን ሁሉ እናደርጋለን። ከሁሉም በፊት ከዚህ ቀደም የሠየምኩት የኮሎኔል ሳንድፎርድ ወታደራዊ ሚሽን፣ ኢትዮጵያ ውስጥ በምሥጢር እየዘለቀ በመግባት የጠላት አቅምና ስትራቴጂ፣ እንዲሁም የሕዝቡ የነፃነት እንቅስቃሴ እስከምን ድረስ እንደሆነ፣ መረጃዎቹን መሰብሰብ አለበት። ከፋሽስት ጋር ለመዋጋት ለሚዘጋጀው ለትልቁ የጦር ፕላን፣ መሠረቱ እነዚህ መረጃዎች ናቸው።

ግርማዊነትዎ ካቀረበልኝ ዋና ዋና ጉዳዮች ውስጥ፣ በሱዳን አካባቢ አገሮች የሚገኙት ኢትዮጵያውያን አርበኞችና ስደተኞች ወደዚህ መጥተው የጦር ሥልጠና እንዲሰጣቸው የማድረግ ጉዳይ ነው። ለዚህ ችግሩ የትራንስፖርቱ ሁኔታ ብቻ ሳይሆን፣ እነዚህ ሰዎች ሱዳን ከመጡ በኋላ የማረፊያቸው ካምፕና የስንቃቸው ጉዳይ በዝርዝር ተጠንቶ መታወቅና መዘጋጀት አለበት። ሐሳቡ የሚደገፍና ውጤት ይሰጣል ተብሎ የሚታመን ስለሆነ፣ በበኩሌ የሚቻለውን እንደማደርግ አረጋግጥልዎታለሁ። ከዚህ ሌላ፣ ግርማዊነትዎን በምክርና በሥራ እንዲረዱ፣ ከኢየሩሳሌምና ከግብፅ ለማስመጣት ያሰቧቸውን ታላላቅ ሰዎች ዝርዝራቸውን እንዲያስታውቁኝ እየጠየቅኩ፣ በተቻለ ፍጥነት እንዲመጡልዎ አደርጋለሁ። ... "

እንግዲህ ! ዝርዝሩ ከዚህ በላይ እንደተገለጸው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ ከዋናው የጦር አዛዥ ከጄኔራል ዌቨል ጋር ተገናኝተው የተለዋወጧቸው ሐሳቦች፣ መንፈሳቸውን ከነበረበት ወደተሻለ ሁኔታ የሚለውጥ ሆኗል። ከዚህ በፊት እንደተነገረው፣ ጃንሆይ ከሎንደን ወደ ሱዳን ከመጡበት ጊዜ ጀምሮ ያጋጠሟቸው ፈተናዎች ብዙዎች ናቸው። ኋላ እንደታየው ከሎንደን ሲነሡ የተነገራቸው ሁሉ፣ ወደ ሱዳን ሳይተላለፍ እዚያው ሎንደን ቀርቷል። ስሕተቱ የተፈጠረው፣ በጠቅላይ ሚኒስትሩና በጦር ሚኒስትሩ ልዩ ካቢኔ ውስጥ ለኢትዮጵያ ጉዳይ ኃላፊዎች የሆኑት ሰዎች፣ ለንጉሠ ነገሥቱ ከሎንደን እስከ ካርቱም የሚጓዙበትን ትራንስፖርት ሲያዘጋጁና በመጨረሻም በወግ ሲሸኟቸው፣ ወደ ካርቱም የመጡበትን ጉዳይና የሚደረግላቸውም እርዳታ ምን እንደሆነ፣ ለአገረ ገዥውና ለጦር አዛዡ ሳያስታውቁ ዝም ማለታቸው ነው። እርግጥ ነው! በነጄኔራል ፕላት በኩል ቅንነት ቢኖር ኖሮ፣ ጃንሆይ የመጡበትን ጉዳይ ከሎንደን ጠይቆ መረዳት

በቻሉ ነበር። ነገር ግን የእነ ፕላት መሠረታዊ ዕምነት፣ ፋሽስትን ከኢትዮጵያ ግዛት ማባረርና አገሪቱን መያዝ የታላቋ ብሪታንያ ኃላፊነት እንጂ፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴን አይመለከትም የሚል ስለሆነ፣ ጠማማውን ትተው ቀናውን መንገድ ለመከተል የሚፈልጉ አልነበሩም። ተደጋግሞ እንደተጠቀሰው፣ ጃንሆይ በበኩላቸው ያሳደሩት ተስፋና ዕምነት፣ ካርቱም ላይ ተዘጋጅቶ የሚጠብቃቸውን ጦር ለመረከብና ዘመቻውን ለመጀመር ስለነበረ፣ ይህ ሁሉ ቀርቶ ያለ አንዳች ዝግጅት ምድረ በረሃ በሆነው ዋዲ ሐልፋ ላይ እንዲያርፉ ሲደረግ፣ የተሰማቸው ኃዘንና የደረሰባቸው መጉላላት ምን ያህል ከባድ መሆኑን መገመት ይቻላል።

ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በተፈጥሮአቸው ችግርን የመመከትና የመታገሥ ችሎታ ያላቸው በመሆናቸው፣ ጠላቶቻቸውን ላለማስደሰት፣ ሥቃዩ የከበዳቸው መስለው አልታዩም። ከጥቂት ሳምንታት በኋላ፣ እንደ እሥረኛ በሩ ከተዘጋባቸው ከዋዲ ሐልፋ ተነሥተው ወደ ካርቱም ሲመጡም፣ እነ ፕላት የበለጠ ችግር ላይ ይጥሏቸው ይሆን ወይ? ተብሎ ተፈርቶ ነበር። ነገር ግን ከካይሮ ጃንሆይን በአማካሪነት እንዲረዳ ተመድቦ አብሮአቸው የመጣው ቻፕማን አንድርውስ፣ እስካሁን በንጉሠ ነገሥቱ ላይ የሚፈጸመው ድርጊት ሁሉ በኃላፊነት የሚያስጠይቅ መሆኑን በግልጽ ይናገር ስለነበረ፣ ኮሎኒያሊስቶቹ እነ ፕላት ምንም ማድረግ አልቻሉም። ሆኖም፣ ንጉሠ ነገሥቱ የመጡበትን ጉዳይ በጥሞና ላለማዳመጥና የሚያስፈልጋቸውንም ለመፈጸም እምቢተኛነታቸውን በግልጽ አሳይተዋል።

በዚህ በሦስተኛው ምዕራፍ ላይ እንደተገለጸው፣ ከመካከለኛው ምሥራቅ ጦር አዛዥ ከጄኔራል ዌቭል ጋር ያደረጉት ንግግር፣ በጣም ጠቃሚና ተስፋም የሚሰጥ በመሆኑ ንጉሠ ነገሥቱ አንድ ዓይነት እርካታ ተሰምቷቸዋል። ዌቭል የነገራቸው ሁሉ እውነትና ምንም ዓይነት የመደለል ሁኔታ የሌለበት መሆኑን በግልጽ ያሳያል። ለምሣሌም ያህል፣ በፋሽስት ላይ ዘመቻውን ለመጀመር የስድስት ወራት ዝግጅት ይጠይቃል ሲላቸው፣ ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ በጣም ጭለማ ሆኖ ታይቷቸው ነበር። በመጨረሻው ዌቭል ከልብ የመነጨ አስተያየቱን ሲገልጽ፣ ዘመቻውን ፈጥኖ በመጀመር ፈጥኖ ከመሸነፍ፣ የስድስት ወራት የተሟላ ዝግጅት አድርጎ ድልን መጐናጸፍ አይሻልም ወይ? ሲል የተናገረውን ቀዳማዊ ኃይለሥላሴ የተቀበሉት ከፍ ባለ መልካም ስሜት ነው። ስለዚህም ዌቭል በገለጹላቸው ሐሳብና በሰጣቸው ተስፋ መሠረት፣ ንጉሠ ነገሥቱ ጉዳዩን በትዕግሥት ከመከታተልና ጊዜውን ከመጠበቅ በስተቀር ሌላ አማራጭ አልነበራቸውም።

**Reference:** FO-371-27516